## ምዕራፍ ፭
### ጉባኤ

፩ ፤ ወሞተ ፡ ረዓይትኒ ፡ እንተ፡ ኀበ ፡ ወጽኡ ፡ መናፍስት ፡ እምነ ፡ ነፍስተ ሥጋሆሙ ፡፡
ከደቂቀ ፡ ሴት ፡ የተወለዱ ፡ በየ ወጡበት ፡ የሚሆን ፡ የረዓይት ሞታቸው፡

፪ ፤ ለይኩን ፡ ዘይማስን ፤
ሙስን ፡ ሞት ፡ ነው ፤ እንድም ፡ ከደቂቀ ፡ ሴት ፡ የተወለዱ ፡ በየወ ጡበት ፡ የሚሆን ፡ የረዓይት ፡ ሞታቸው ፡ ሥጋቸው ፡ ይፈርስ ፡ ይበሰብስ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤ አን ድም ፡ ከደቂቀ ፡ ሴት ፡ የተወለዱ ፡ የረዓይት፡ሞታቸው በየወጡበት፡ ነው ፤ ያው ፡ ግን ፡ ሥጋቸው ፡ የሚፈርስ ፡ የሚበሰብስ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤

፫ ፤ ወዘእንበለ ፡ ይኩን ፡ ኵነኔ ፡ ከማሁ ፡ ይማስኑ ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ኵነኔ ፡ ዓባይ ፤
እስከ ፡ ዕለተ ፡ ተፍጻሜት ፡ ዓባይ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ፍጹም ፡ ፍርድ ፡ ሳይሆን፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ምጽአት ፤ እንዲሁ ፡ ይጠፋሉ ፤
እምዓለም ፡ ዓቢይ ፤
ዓለም ፡ ገሃነም ፡ ለኃጥአን ፡ ከመሰ ጠቱ ፡ አስቀድሞ ፤
ይትፈጸም ፡ እምትጉሃን ፡ ወረሲዓን፤
በደቂቀ ፡ ሴት ፡ ፍጹም ፡ ፍርድ ይፈጸማል ፤

፬ ፤ ወይእዜኒ ፡ ለትጉሃን ፡ እለ ፡ ፈነውከ ፡ ትስአል ፡ በእንቲአሆሙ ፡ እለ ፡ ቀዲሙ ፡ በሰማይ ፡ ሀለዉ ፤
በሎሙ ፡ ያለበት ፡ ነው ፤ አሁንም፡ ለእነርሱ ፡ ልትለምንላቸው ፤ የላኩህን ፡ ከዚያ ፡ አስቀድሞ ፡ በደብር ፡ ቅዱስ ፡ የነበሩ ፡ ለኃጢ አት ፡ የሚተጉ ፡ ደቂቀ ፡ ሴትን ፡ እንዲህ፡በላቸው ፤

፭ ፤ ወይእዜኒ ፡ አንትሙ ፡ በሰ ማይ ፡ ሀለውክሙ ፤
ዛሬም ፡ በልዑል ፡ መዓርግ ፡ በደ ብር ፡ ቅዱስ ፡ በሰማያዊ ፡ ግብር፡ አላችሁ ፤
ወኀቡዓት ፡ ዓዲ ፡ ኢተከሥቱ ፡ ለክሙ ፤
ምሥጢረ ፡ ኀባውዕ ፡ ምሥጢረ አጋንንት ፡ አልተገለጡላችሁም ፤

፮ ፤ ወምኑነ ፡ ምሥጢረ ፡ አእመ ርክሙ ፡ ወዘንተ ፡ ዜነውክሙ ፡ ለአን ስት ፡ በጽንአ ፡ ልብክሙ ፤
የተናቀ ፡ ምሥጢርንም ፡ አወቃ ችሁ ፤ በልቡናችሁም ፡ ጽናት ፡ ይህን ፡ ነገር ፡ ለሴቶች ፡ ነገራችሁ ፤

፯ ፤ ወበዝንቱ ፡ ምሥጢር ፡ ያበዝኃ ፡ አንስት ፡ ወሰብእ ፡ እኪተ ፡ ዲበ ፡ ምድር ፡ በሎሙ ፡ እንከሰ ፡ አል ብክሙ ፡ ሰላም ፤
ከላይ ፡ በሎሙ ፡ እንዳለ ፡ በዚህ ፡ ይታወቃል ፤ በዚህም ፡ ምሥጢር ፡

በወንዶችና ፡ በሴቶች ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ክፋትን ፡ ያበዛሉ ፤ እንግ ዲህስ ፡ ፍቅር ፡ አንድነት ፡ የላች ሁም ፡ በላቸው ፡ አለኝ ፡፡

፰ ፡፡ ወነሥኡኒ ፡ ውስተ ፡ ፩ዱ ፡ መካን ፡ ኀበ ፡ ሀለዉ ፡ ህየ ፡ ከመ ፡ እሳት ፡ ዘይነድድ ፡፡

እንደ ፡ እሳት ፡ የሚነድ ፡ ደቂቀ ሴት ፡ ወደአሉበት ፡ አንድ ፡ ቦታ ፡ ወሰዱኝ ፡ አለ ፤ መካነ ፡ ኃጥ አን ፡፡ አንድም ፡ ስነ ፡ ፍጥረት ፡፡

ወሶበ ፡ ይፈቅዱ ፡ ያስተርእዩ ፡ ከመ ሰብእ ፡፡

ከመ ፡ እሳት ፡ ብሎ ፡ ነበርና ፡ ሰዎች ፡ ናቸው ፡ ለማለት ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ይታያሉ ፡ አለ ፡፡ አንድም ፡ ለንጹሬ ፡ የበቁ ፡ ጻድቃን ፡ ሊያዩ ዋቸው ፡ በወደዱ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ያዩዋቸዋል ፡፡

፱ ፡፡ ወወሰዱኒ ፡ ውስተ ፡ መካን ፡ ዘአውሎ ፡ ወውስተ ፡ ደብር ፡ ዘከተማ ፡ ርእሱ ፡ ይበጽሕ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፤

ጥልቅ ፡ ነፋስ ፡ ወዳለበት ፡ ቦታ ወሰዱኝ ፡፡ ጫፉ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ የሚደርስ ፡ ተራራ ፡ አየሁ ፡፡ ስነ ፡ ፍጥረት ፡ ነው ፡፡ አንድም ፡ መካነ ፡ ኃጥአን ፡ ላገኛቸው ፡ መከራ ፡ ፍጻሜ ፡ እንደ ፡ ሌለው ፡ ለማ ጠየቅ ፡፡

፲ ፡፡ ወርኢኩ ፡ ፩ተ ፡ መካናተ ፡ ብሩሃተ ፡፡

አንድ ፡ መካነ ፡ ኃጥአንን ፤ ሦስ ቱን ፡ መካነ ፡ ጻድቃንን ፡ አየሁ ፡፡ ሦስት ፡ አለ ፡ ባለ ፡ መቶ ፤ ባለስሳ ፤ ባለ ፡ ሠላሳ ፡ ስለኖረባት ፡፡ አንድም ፡ ወጣኒ ፤ ማዕከላዊ ፤ ፍጹማዊ ፡ ስለኖረባት ፡ መካነ ፡ ኃጥአንን ፡ ብሩህ ፡ አለው ፡ በጻድቃን ፡ አስጠ ግቶ ፡፡

ወነጐድጓድ ፡ ውስተ ፡ አጽናፍ ፡፡

በመካነ ፡ ጻድቃን ፡ አጠገብ ፡ ባለ ፡ በመካነ ፡ ኃጥአን ፡ ነጐድጓድ ፡ አለ ፡፡

ወኀበ ፡ ዕመቁ ፡ ቀስተ ፡ እሳት ፤

በጥልቀነቱ ፡ ዘንድ ፡ ቀስተ ፡ እሳት ፡ አለ ፡፡

ወሐፅ ፡ ወምጕንጳቲሆሙ ፡፡

የኃጥአን ፡ ጕራንጕሬያቸው ፡ አለ ፡፡ ሰይፈ ፡ እሳት ፡ መባርቅት አለ ፤ መቅሠፍተ ፡ ኃጥአንን ፡ በምሳሌ ፡ ያሳየዋል ፡፡

ወሰይፈ ፡ እሳት ፡ ወመባርቅት ፡ ኵሉ ፡፡

የእሳት ፡ ሰይፍ ፡ መብረቆችም ሁሉ ፡ አሉ ፡፡

፲፩ ፡፡ ወነሥኡኒ ፡ እስከ ፡ ማየ ፡ ሕይወት ፡ ዘይትናገር ፡፡

ድምጽ ፡ ያለው ፡ የመጣያ ፡ ውኃ ፡ ወዳለበት ፡፡ አንድም ፡ ዘይትነገር ፡ ቢል ፡ በኔ ፡ ቃል ፡ የሚነገር ፡ ማየ ፡ ሕይወት ፡ እስካለበት ፡ ድረስ ፡፡ አንድም ፡ በሰው ፡ አድሮ ፡ የሚናገር ፡ ማየ ፡ ሕይወት ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡፡ አንድም ፡ ዘይትነገር ፡ በኔ ፡ ቃል ፡ የሚነገር ፡ ማየ ፡ ሕይወት ፡ መን ፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እስከሚሠጥበት ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ አደረሱኝ ፡፡

ወእስከ ፡ እሳተ ፡ ዓረብ ፤

በምዕራብ ፡ እስከ ፡ አለው ፡ ብርሃን ፡ ድረስ ፡ ወሰዱኝ ፡

ዘውእቱ ፡ ይእኅዝ ፡ ኵሉ ፡ ዕርበተ ፡ ፀሐይ ።

ይኸውም ፡ የፀሐይን ፡ መግቢያ ሁሉ ፡ የሚይዝ ፡ ነው ።

፯ ። ወመጻእኩ ፡ እስከ ፡ ፈለገ ፡ እሳት ፡ ዘይውኅዝ ፡ እሳቱ ፡ ከመ ፡ ማይ ።

እሳቱ ፡ እንደ ፡ ፈሳሽ ፡ ውኃ ፡ ሆኖ ፡ ውቅያኖስ ፡ ሲገባ ፡ ያየዋል ። ስነ ፡ ፍጥረት ። አንድም ፡ መካነ ፡ ኃጥአን ፡ ላገኛቸው ፡ መከራ ፡ ፍጻሜ ፡ እንደሌለው ፡ ለማጠየቅ ።

ወይትከአው ፡ ውስተ ፡ ባሕር ፡ ዓቢይ ፡ ዘመንገለ ፡ ዓረብ ።

በምዕራብ ፡ ወዳለው ፡ ባሕር ፡ ሲፈስስ ፡ አየሁ ።

፰ ። ወርኢኩ ፡ ኵሉ ፡ ዓበይተ ፡ አፍላገ ፡ ወእስከ ፡ ዓቢይ ፡ ጽልመት በጻሕኩ ።

ጽኑ ፡ ጨለማ ፡ በርባሮስ ፡ እስካለበት ፡ ድረስ ፡ ደርሼ ፡ ታላላቅ ፡ ወንዞችን ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ።

ወሖርኩ ፡ ኀበ ፡ ኵሉ ፡ ዘሥጋ ፡ ያንሶሱ ።

ሥጋዊ ፡ ደማዊ ፡ ሁሉም ፡ ወደ ሚመላለስበት ፡ ሄድኩ ።

፱ ። ወርኢኩ ፡ አድባረ ፡ ቆባራት ዘክረምት ።

በክረምት የሚገኙ ፡ ጭጋጎች ፡ ያሉባቸው ፡ ተራሮችን ፡ አየሁ። አንድም ፡ በክረምት ፡ የሚገኝ ፡ የጉም ፡ ተራራ ፡ አየሁ ።

ወምክዓወ ፡ ማይ ፡ ዘኵሉ ፡ ቀላይ ።

ውኃ ፡ የሚፈስበትን ፡ ሁሉ ፡ አየሁ ።

፲ ። ወርኢኩ ፡ አፉሆሙ ፡ ለኵሉሙ አፍላገ ፡ ምድር ።

የዚህ ፡ ዓለም ፡ ውኃ ፡ ሁሉ ፡ የሚገባበትን ።

ወአፉሃ ፡ ለቀላይ ።

ውቅያኖስ ፡ የምትቀበልበትን ፡ አየሁ ።

፲፩ ። ወርኢኩ ፡ መዛግብተ ፡ ኵሉ ፡ ነፋሳት ።

አራቱ ፡ ነፋሳት ፡ የሚወጡበትን ፡ የሚገቡበትን ፡ አየሁ ።

ወርኢኩ ፡ ከመ ፡ በሙ ፡ አሠርገወ ፡ ኵሉ ፡ ፍጥረተ ።

አጽንዖ ፡ ሲል ፡ ነው ። በሳቸው ፡ ፍጥረትን ፡ ሁሉ ፡ እንዳጠና ፡ አየሁ ።

ወመሠረታቲሃ ፡ ለምድር ።

የምድርን ፡ መሠረት ፡ አየሁ ፡ አለ ። ከታች ፡ ነፋስ ። ቀጥሎ ፡ እሳት ። ቀጥሎ ፡ ውኃ ። ቀጥሎ ፡ መሬት ነውና ።

፲፪ ። ወርኢኩ ፡ ዕብነ ፡ ማዕዘንተ ምድር ።

ምድር ፡ የጸናበት ፡ በአራቱ ፡ ማዕዘን ፡ ያለ ፡ አድማስን ፡ አየሁ ።

ወርኢኩ ፡ ፬ተ ፡ ነፋሳተ ፡ እለ ፡ ይፀውርዋ ፡ ለምድር ።

ምድርን ፡ እንደ ፡ ካስማ ፡ የያዟትን ። አራቱን ፡ ነፋሳት ።

ወለጽንዓ ፡ ሰማይ ።

ጽንዕት ፡ ሰማይ ፡ ሲል ፡ ነው ።

ሰማይ ፡ የጸናበትንም ፡ አራቱን ነፋሳት ፡ አየሁ ፤

፲፰ ፤ ወርኢኩ ፡ ከመ ፡ ነፋሳት ፡ ይረብብዋ ፡ ለልዕልና ፡ሰማይ ፤

ልዕልት ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ልዕልት ሰማይን ፡ እንደ ፡ ካስማ ፡ የያዟት ፡ ነፋሳትን ፡ እንደ ፡ ምሰሶ ፡ ሁነው ፡ አየሁ ፤

፲፱ ፤ ወእሙንቱ ፡ ይቀውሙ ፡ ማዕከለ ሰማይ ፡ ወምድር ፤

ከእንሳቸውም ፡ በምድርና ፡ በሰ ማይ ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ አዕማድ ፡ (ምሰሶዎች) ፡ ሁነው ፡ ቁመው ፡ አየሁ ፤

ወእሙንቱ ፡ ውእቶሙ ፡ አዕማደ ፡ ሰማይ ፤

እነሳቸውም ፡ የሰማይ ፡ ምሰሶዎች ናቸው ፤

፳ ፤ ወርኢኩ ፡ ነፋሳተ ፡ እለ ፡ ይመ ይጥዋ ፡ ለሰማይ ፤

ሰማይን ፡ የሚሸከሙ ፡ ነፋሳትን አየሁ ፤

ወእለ ፡ ያዐርቡ ፡ ከበበ ፡ ፀሐይ ፡ ወኵሉ ፡ ከዋክብተ ፤

ፀሐይን ፡ ከዋክብትን ፡ የሚያገቡ ፡ ነፋሳትን ፡ አየሁ ፤

፳፩ ፤ ወርኢኩ ፡ ዘዲበ ፡ ምድር ፡ ነፋሳተ ፡ ዘይፀውሩ ፡ ደመናተ ፤

በዚህ ፡ ዓለም ፡ ደመናትን ፡ የሚ ሸከሙ ፡ ነፋሳትን ፡ አየሁ ፤

፳፪ ፤ ወርኢኩ ፡ ፍናወ ፡ መላእክት ፤

ጐልቄ ፡ መላእክት ፡ ሲል ፡ ነው ፤ የመላእክትንም ፡ ቊጥር ፡ አየሁ ፤

ወርኢኩ ፡ ውስተ ፡ ጽንፈ ፡ ምድር ፡ ጽንዐ ፡ ዘሰማይ ፡ መልዕልተ ፤

ጠፈር ፡ በላይ ፡ ሆኖ ፡ የጸናበትን ፡ አድማስን ፡ አየሁ ፤ አንድም ፡ በላይ ፡ ሁኜ ፡ ጠፈር ፡ የጸናበት ፡ አድማስን ፡ አየሁ ፤

፳፫ ፤ ውንለፍኩ ፡ መንገለ ፡ አዜብ ፡ ወይነድድ ፡ መዓልተ ፡ ወሌሊተ ፡ ኀበ ፯ቱ ፡ አድባር ፡ ዘእምዕብን ፡ ክቡር ፤

ውንለፍኩ ፡ መንገለ ፡ አዜብ ፡ ኀበ ፡ ፯ቱ ፡ አድባር ፡ ዘእምዕብን ክቡር ፡ ዘይነድድ ፡ መዓልተ ፡ ወሌሊተ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ በመዓ ልትም ፡ በሌሊትም ፡ የሚያበራ ፡ ነው ፤ ከከበረ ፡ በአዜብ ፡ እኩል ፡ ወዳለ ፡ ተራራ ፡ ሄድኹ ፤ አንድም ፡ የዕንቊ ፡ ተራራ ፡ ወዳለበት ፡ ሄድኹ ፤

፳፬ ፤ ፫ቱ ፡ ዘመንገለ ፡ ጽባሕ ፡ ወ፫ቱ ፡ ዘመንገለ ፡ አዜብ ፤

ሦስቱ ፡ በምሥራቅ ፡ በኩል ፤ ሦስቱ ፡ በዓዜብ ፡ በኩል ፡ ናቸው ፤

ወዘመንገለ ፡ ጽባሕስ ፡ ዘእምዕብነ ፡ ኅብር ፤

ከሦስቱ ፡ አንዱ ፡ ብዙ ፡ መልክ ካለው ፡ ዕንቊ ፡ ወገን ፡ ነው ፤

ወ፩ዱ ፡ ዘእምዕብነ ፡ ባሕርይ ፤

አንዱ ፡ ባሕርይ ፡ ከሚባል ፤

ወአሐዱኒ ፡ ዘእምዕብነ ፡ ፈውስ ፤

አንዱ ፤ ደመ-ረጭ ፤ (ደመአርድ)፡ የሚባል ዕንቊ ፡ ያለበት ፡ ነው ፤

ወዘመንገለ ፡ አዜብ ፤

በምዕራብ ፡ በኵል ፡ ያለው ፡
ሦስቱ ፡ ሁሉ ፤

እምዕብን ፡ ቀይሕ ፤
የቀይ ፡ ዕንቍ ፡ ተራራ ፡ ነው ፤
አንድም ፡ ቀይ ፡ ዕንቍ ፡ ያለበት
ተራራ ፡ ነው ፤

፳፭ ፤ ወማዕከላይሰ ፡ ይጐድዕ ፡
እስከ ፡ ሰማይ ፡ ከመ ፡ መንበሩ ፡
ለእግዚአብሔር ፡ ዘእምዕብነ ፡ ፔካ ፤

ወማዕከላይሰ ፡ ዘእምዕብነ ፡ ፔካ ፡
ሲል ፡ ነው ፤ ፔካ ፡ ከሚባል ፡
ዕንቍ ፡ ወገን የሚሆን ፡ መካከለ
ኛው ፡ ተራራ ፤ ይጐድዕ ፡ ይበጽሕ ፡
ይሰክፍ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ሲል ፡
ነው ፤ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ይደርሳል ፤
ከመ ፡ መንበሩ ፡ ሲል ፡ እንደ ፡
እግዚአብሔር ፡ ዙፋን ፤ አንድም ፡
የእግዚአብሔር ፡ ዙፋን ፣ መቀ
መጫ ፡ እንደመሆኑ ፡ እስከ ሰማይ ፡
ይደርሳል ፤

፳፮ ፤ ወድማሁ ፡ ለመንበሩ ፡ ዘእም
ዕብነ ፡ ሰንፔር ፤

ድማሁ ፡ ለመንበር ፣ አጐበሩ ፡ ሰን
ፔር ፡ ከሚባል ፡ ዕንቍ ፡ ወገን ፡
ነው ፤

ወእሳተ ፡ ዘይነድድ ፡ ርኢኩ ፡ ዘሀሉ
ውስተ ፡ ኵሉ ፡ አድባር ፤

በተራራ ፡ ሁሉ ፡ ያለ ፡ የሚነድ
እሳትንም ፡ አየሁ ፡ አለ ፣ በስባት ፡
ተራራ ፡ የሚያበራ ፡ ዕንቍ ፡ አየሁ ፤
ለጊዜው ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ አይቷል ፤
ለኋላው ፡ ምሳሌ ፡ ነው ፤ ስድስት ፡
ተራራ ፡ የዓለመ ፡ ፍጡራን ፤
ዘእምዕብነ ፡ ኀብር ፡ ያለው ፡ ከብዙ ፡
ሪም ፡ ያላቸው ፡ ጻድቃን ፡ እንደ ፡
ዮሐንስ ፡ እርሱ ፡ ከነቢያት ፡ ነቢይ ፣
ከደናግል ፡ ድንግል ፣ ከሰማዕታት ፡
ሰማዕት ፣ ከሐዋርያት ፡ ሐዋርያ ፡
ነውና ፤ ባሕርይ ፡ ሳይበድሉ ፡ የቀሩ ፡
እንደ ፡ ኤልያስ ፡ እንደ ፡ ኤርምያስ ፡
ያሉት ፤ ቀደስኩከ ፡ እምከርሠ ፡
እምከ ፡ ወዘእንበለ ፡ ትጻእ ፡ እማ
ኀፀን ፡ ሜምኩከ[፩] ፡ እንዲል ፤ ዘእ
ምዕብነ ፡ ፈውስ ፡ በድለው ፡ የተ
መለሱ ፡ እንደ ፡ አዳም ፣ እንደ ፡
ዳዊት ፣ እንደ ፡ ጴጥሮስ ፡ ያሉት ፤
ቀይሕ ፡ ያለው ፡ ሰማዕታት ፣ ደማ
ቸውን ፡ ያፈሰሱ ፣ ከእሳት ፡
ይወድቃሉና ፤ ማዕከላይ ፡ ያለው ፡
የዓለመ ፡ ፈጣሪ ፤ ይበጽሕ ፡ አለው ፣
ከዓለመ ፡ ፍጡራን ፡ ዓለመ ፡
ፈጣሪ ፡ ይበልጣልና ፤ አንድም ፡
ስድስቱ ፡ በ፮ቱ ፡ ቃላተ ፡ ወንጌል ፡
ያመኑ ፡ ምዕመናን ፤ ማዕከላይ ፡
ይበጽሕ ፡ ያለው ፣ የእመቤታችን ፣
የእግዚአብሔር ማደሪያ ፡ እንደ ፡
መሆንዋ ፡ መልዕልተ ፡ ፍጡራን ፡
መትሕተ ፡ ፈጣሪ ፡ ናትና ፤

፳፯ ፤ ወርኢኩ ፡ ሀየ ፡ መካነ ፡
ማዕዶቱ ፡ ለዓቢይ ፡ ምድር ፤

የአድማስ ፡ መጨረሻ ፡ ውቅያኖስን
አየሁ ፤
ሀየ ፡ ይትጋብኡ ፡ ማያት ፤
ውኃዎች ፡ በዚያ ፡ ይሰበሰቡበታል ፤

፳፰ ፤ ወርኢኩ ፡ ንቅዓተ ፡ ምድር ፡
ዕሙቀ ፡ በአዕማዲሁ ፡ ለእሳተ ፡ ሰማይ ፤

በሰማይ ፡ እሳት ፡ ምሰሶዎች ፡
ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ የምድር ፡ ጉድ

፩ ኤር. ፩፥፭ ፤

ጓድ : አየሁ : አለ ፣ በሰማይ : እሳት : የሚቃጠሉ : ደቂቀ : ሴት : ያሉበት : ጥልቅ : የሚሆን : ገሃነ ምንም : አየሁ ፤

፳፱ ፤ ወርኢኩ : በውስቴቶሙ : አዕማደ : ሰማይ : ዘእሳት : ዘይወርዱ ፣

በእሳት : የሚቃጠሉ : ወደጥልቅም : የሚወርዱ : በውስጣቸው : ደቂቀ : ሴትን : አየሁ ፣

ወአልቦሙ : ኍልቍ : ኢመንገለ : መልዕልት : ወኢመንገለ : ዕመቅ ፣

ስፍር : ቍጥር : የላቸውም ፤ አንድም : ለሚያገኛቸው : መከራ ፍጻሜ : የለውም ፤ አንድም : መልዕልት : ወደላይ : ሰማይ : ወደታች : መሠረት : የለውም ለሚያገኛቸውም : መከራ : ፍጻሜ : እንደሌለው : ለማጠየቅ ፤

፴ ፤ ወዲበ : ውእቱ : ንቅዓት : ርኢኩ : መካነ ፣

በጕድጓዱ : ላይ : ቦታ : አየሁ ፤

ወኢጽንዓ : ሰማይ : ላዕሌሁ : ወኢመሠረተ : ምድር : በታሕቴሁ ፣

ወደ : ላይ : ጠፈር ፣ ወደታች መሠረት : የለውም : ለሚያገኛቸውም : መከራ : ፍጻሜ : እንደሌለው : ለማጠየቅ ፤

፴፩ ፤ ወኢማይ : እልቦ : ላዕሌሁ : ወኢአዕዋፍ : አላ : መካነ : በድው : ውእቱ ፣

ምድረ : በዳ : ነው : እንጂ ፣ ውኃ : አዕዋፍ : የሉበትም ፤ አንድም : ከረድኤት ፣ ከጻድቃን ፣ ከመላእክት : ምድረ : በዳ : ነው : እንጂ ፣ ረድኤት ፣ መላእክት ፣ ጻድቃን ፣ የሉበትም ፣

፴፪ ፤ ወማሩመ : ርኢኩ : በህየ : ፯ተ : ከዋክብተ : ከመ : ዓበይት : አድባር : ዘይነድዱ ፤

እሳት : እንደ : ተያያዘው : ተራራ : የሚነዱ : ሰባት : ከዋክብትን : አየሁ : አለ ፣ ደቂቀ : ሴትን : አየሁ ፤ ሰብአተ : አላቸው ፣ በፍጹም : ቁጥሮ : ነው ፤ ከዋክብት : አላቸው ፣ በጥንተ : ግብራቸው : ነው ፤ ከዋክብትን : ያመልኩ : ነበርና ፤

፴፫ ፤ ወከመ : መንፈስ : ዘይሴአለኒ : ይቤ መልአክ ፣

የሚጠይቀኝ : መልአክ : ባልደረባዬ : እንደመሆኑ : እንዲህ : አለ ፤

ዝውእቱ : መካነ : ተፍጻሜቱ : ለሰማይ : ወለምድር ፤

ይህ : ቦታ : የምድርና : የሰማይ መጨረሻ : ቦታ : ነው : አለ ፤

፴፬ ፤ ቤተ : ሞቅሕ : ኮናሙ : ዝንቱ ፤

የሰማይ ፣ የምድር : ፍጻሜ : የሚሆን : ይህ : ቦታ : ለደቂቀ : ሴት : የግዞት : ቦታ : ሆናቸው ፤ የሚያሳየው : በመጨረሻው : በምዕራብ : ነውና ፤ አንድም : የሰማይ ፣ የምድር : ፍጻሜ : የሚሆን : ሰማይ : ያይደለ ፣ ምድርም : ያይደለ : ይህ : ቦታ ቤተ : ግዞት : ሆናቸው ፤ በኀ

ዋው ፡ ሁነው ፡ ያሳየዋልና፤ ለከ
ዋክብተ ፡ ሰማይ ፡ ወሰኃይለ ፡
ሰማያት ፤ ለሰማይ ፡ ጭፍራ ፡
ከዋክብት ፡ ለነበሩ ፡ ለደቂቀ ፡
ሴት ፡ የግዞት ፡ ቤት ፡ ሆናቸው፤
ወከዋክብት ፡ እለ ፡ ያንኰረኲሩ ፡
ዲበ ፡ እሳት ፤
በእሳት ፡ ውስጥ ፡ ለሚገለባበጡ
ኮከቦችም ፡ ይህ ፡ የግዞት ፡ ቤት
ሆናቸው ፤
፴፭ ፤ ወእሉ ፡ እሙንቱ ፡ እለ ፡
ኀለፉ ፡ ትእዛዘ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምቅ
ድመ ፡ ጽባሖሙ ፤
እነርሱም ፡ በእውቀት ፡ በደግነት ፡
ፍጹም ፡ ከመሆናቸው ፡ አስቀድሞ፤
እስመ ፡ ኢመጽኡ ፡ በጊዜሆሙ ፤
በጊዜያቸው ፡ ጊዜ ፡ አልመጡምና ፤
እንድም ፡ በጊዜያቸው ፡ ጊዜ ፡ አል
መጡምና ፡ ምንም ፡ ባይመጡ ፡
ተምዖሙ ፡ ብለህ ፡ ወደታች ፡
እሠር ፤
፴፮ ፤ ወተምዖሙ ፡ ወአሠሮሙ ፡
እስከ ፡ ጊዜ ፡ ተፍጻሜተ ፡ ኃጢአቶሙ ፤
በኃጢአታቸው ፡ የመጣባቸው ፡
ፍዳ ፡ እስኪፈጸምባቸው ፡ ድረስ
ተቆጥቶ ፡ አጋዛቸው ፤
በዓመተ ፡ ምሥጢር ፤
ዓቢይ ፡ ዓለም ፡ መንግሥተ ፡
ሰማይ ፤ ለጻድቃን ፡ ዓቢይ ፡ ዓለም፤
ገሃነመ ፡ እሳት ፡ ለኃጥአን ፡ የሚሰ
ጥበት ፡ ነውና ፡ ምሥጢር ፡ አለው፤
፴፯ ፤ ወይቤለኒ ፡ ዑርኤል ፡ በዝየሰ ፡
ተደሚሮሙ ፡ መላእክት ፡ ምስለ ፡
አንስት ፤

ዑራኤልም ፡ በዚህ ፡ በቦታው ፤
እንድም ፡ በግብሩ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፡
ከሴቶች ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ሁነው ፤
ይቀውሙ ፡ መናፍስቲሆሙ ፤
ነፍሶቻቸው ፡ በገሃነም ፡ ይኖራሉ ፡
አለ ፤
፴፰ ፤ ወብዙኀ ፡ አርአያ ፡ ከዊኖሙ ፡
አርኰስዎሙ ፡ ለሰብእ ፤
በብዙ ፡ ወገን ፡ እብነት ፡ ሁነው
ሰዎችን ፡ አረከሷቸው ፤ እንድም
አርኰስዎሙ ፡ ብዙኀ ፡ አርአያ ፡
ብዙኀ ፡ ብሎ ፡ ይገጥሟል ፤ አብነት ፡
ሁነው ፡ ፈጽመው ፡ አረከሷቸው ፤
ወያስሕትዎሙ ፡ ለሰብእ ፡ ከመ ፡
ይሡዑ ፡ ለአጋንንት ፡ ከመ ፡ አማልክት ፤
ምዕመናን ፡ ለሥላሴ ፡ እንዲሠዉ ፡
እነሱም ፡ ለጣዖታት ፡ ሠዉ ፤
እስመ ፡ በዕለት ፡ ዓባይ ፡ ኮነኔ ፡ በዘይ
ትኴነኑ ፡ እስከ ፡ ይትፈጸሙ ፡ በዕለት ፡
ዓባይ ፤
ታላቅ ፡ በሆነች ፡ ቀን ፡ እስኪያጠ
ፋአቸው ፡ ድረስ ፡ ጽኑ ፡ ፍርድ ፡
በሚፈረድባት ፡ በዕለተ ፡ ምጽአት ፡
በሚፈረድባቸው ፡ ገንዘብ ፡ ይፈረ
ድባቸዋልና ፡ ይሠዋሉ ፤
፴፱ ፤ ወአንስትያሆሙኒ ፡ እስሒ
ቶን ፡ መላእክተ ፡ ሰማይ ፡ ከመ ፡ ሰላ
ማውያት ፡ ይከውና ፤
ሴቶቻቸውም ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ማዕ
ረግ ፡ የነበሩ ፡ የሴትን ፡ ልጆች ፡
አስተው ፡ እንደ ፡ ደኅና ፡ ይሆ
ናሉ ፤ ሴት ፡ መነኰሲት ፡ ወን
ዱን ፡ መነኰሴ ፡ አስታ ፡ ደኅነኛ ፡
እንድትመስል ፤

## ጉባኤ

፫ ፤ ወእነ ፡ ሄኖክ ፡ ርኢኩ ፡ አር
ዐያ ፡ ባሕቲትየ ፤
እኔ ፡ ሄኖክ ፡ የብቻዬን ፡ ነገር
የብቻዬን ፡ ምሥጢር ፡ አየሁ፤
አንድም ፡ ሳይናበብ ፡ ብቻዬን ፡
ምሥጢር ፡ አየሁ ፤
አጽናፈ ፡ ኵሉ ፤
በጽንፈ ፡ ምድር ፡ ያለውን ፡ ሁሉ ፡
አየሁ፤
ወአልቦ ፡ ዘርእየ እምሰብእ ዘከመ ፡
አነ ፡ ርኢኩ ፡
እኔ ፡ እንዳየሁት ፡ ያየ ፡ የለም
አለ፤ ራእዩ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ነውና፤
አንድም ፡ እርሱ ፡ ያየውንም ፡
ያየ ፡ የለምና ።

## ምዕራፍ ፳

፩ ፤ ወዝንቱ ፡ ውእቱ ፡ አስማተ
ሆሙ ፡ ለእለ ፡ ይተግሁ ፡ ቅዱሳን ፡
መላእክት፤
ለቅዳሴ ፤ ለተልዕኮ ፤ ለተራድኦ
የሚተጉ ፤ የቅዱሳን ፡ መላእክት ፡
ስማቸው ፡ ይህ ፡ ነው ፤
፪ ፤ ዑራኤል ፡ ፩ዱ ፡ እመላእክት
ቅዱሳን ፤
ከከበሩ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡
ዑራኤል ፡ ነው ፤ ዑራኤል ፡ ማለት ፡
ብርሃነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ማለት ፡
ነው ፤
እስመ ፡ ዘረዓም ፡ ወዘረዓድ ፤
በመብረቅ ፡ በነጐድጓድ ፡ የተሾመ ፡
ነውና ፤

፫ ፤ ሩፋኤል ፡ ፩ዱ ፡ እመላእክት ፡
ቅዱሳን ፡ ዘመናፍስተ ፡ ሰብእ ፤
ከሊቃን ፡ መላእክት ፡ አንዱ ፡
ሩፋኤል ፡ ነው ፤ ሩፋኤል ፡ ማለት ፡
ፈውስ ፡ እግዚአብሔር ፡ ማለት ፡
ነው ፤ ዘመናፍስተ ፡ ሰብእ ፡ አለው ፡
በሰው ፡ ነፍሳት ፡ ወይም ፡ በሰው ፡
ቍስል ፡ የተሾመ፤
፬ ፤ ራጉኤል ፡ አሐዱ ፡ እመላእክት፡
ቅዱሳን ፤
ከከበሩ ፡ መላእክት ፡ አንዱ ፡
ራጉኤል ፡ ነው ፤ ራጉኤል ፡ ማለት ፡
ራእየ ፡ እግዚአብሔር ማለት ፡
ነው ፤
ዘይትቤቀሉ ፡ ለዓለም ፤
ይህን ፡ ዓለም ፡ የሚያሳልፍ ፤
ወለብርሃናት ፤
ፀሐይን ፡ ጨረቃን ፡ የሚያሳልፍ፤
ፍጡራንንስ ፡ በፍጡር ፡ እጅ ፡ አያ
ሳልፋቸውም ፡ ብሎ ፡ ዲያብሎስን ፡
የሚበቀል ፤
ወለብርሃናት ፤
አጋንንትን ፡ የሚበቀል ፤ እስመ
ለሊሁ ፡ ሰይጣን ፡ ይትሜሰል ፡
ከመ ፡ መልአከ ፡ ብርሃን ፡ እንዲል[፩] ፤
አንድም ፡ ህየንተ ፡ ብርሃናት ፡ ቢል ፡
ስለ ፡ ጻድቃን ፡ ዲያብሎስን ፡ የሚ
በቀል ፤
፭ ፤ ሚካኤል ፡ አሐዱ ፡ እመላእክት ፡
ቅዱሳን ፤
ከሊቃን ፡ መላእክት ፡ አንዱ ፡ ቅዱስ ፡
ሚካኤል ፡ ነው ፤ ሚካኤል ፡ ማለት፡
መሐሪ ፡ ወመስተሣህል ፡ ማለት ፡
ነው ፤ ዕፁብ ፡ ነገርም ፡ ይለዋል ፤

፩ ፤ ፪ኛ ቆሮ. ፲፩ ፡ ፲፬

እስመ ፡ በዲበ ፡ ሠናይቱ ፡ ለሰብእ ፡ ተአዛዚ ፡ ዲበ ፡ ሕዝብ ።
ጌታ ፡ በሚያደርገው ፡ ቸርነት ፡ ላይ፣ ለሰብእ ፣ ለሕዝብ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ነው ። ለሰው ፡ ታዛዥ ፡ ነውና ። ለሰው ፡ በሚያደርገው ፡ በጎነቱ ፡ ላይ ፡ ለሕዝቡ ፡ ታዛዥ ፡ ነውና።

፮ ። ሠረቃኤል ፡ አሐዱ ፡ እመላእ ክት ፡ ቅዱሳን ።
ከከበሩ ፡ የከበረ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡ ሠረቃኤል ፡ ነው ። የዚህ፡ ስሙ ፡ አልተተረጐመም ። አን ድም ፡ ፀዋሬ ፡ ስም ፡ ሠረቀ ፡ በሥጋ ፡ ወሀቤ ፡ አእምሮ ፡ ማለት ፡ ነው ።
ዘዲበ ፡ መናፍስተ ፡ ዕጓለ ፡ እመ ሕያው ፡ ዘመናፍስተ፡ የኀጥእ ፣
አእምሮ ፡ ባጡ ፡ ሰዎች ፡ ላይ የተሾመ ።

፯ ። ገብርኤል ፡ አሐዱ ፡ እመላእ ክት ፡ ቅዱሳን ።
ከከበሩ ፡ ከሊቃነ ፡ መላእክት ፡ አንዱ ፡ ገብርኤል ፡ ነው ። ገብርኤል፡ ማለት ፡ አምላክ ፡ ወሰብእ ፡ ማለት ፡ ነው ።
ዘዲበ ፡ አኪስት ።
አጋንንት ፡ መርዝ ፡ እንዳይበጠ ብጡ ፡ በምንጭ ፡ ላይ ፡ የተሾመ ።
አክይስት ፡ ቢል ፡ በእባቦች ፡ ላይ ፡ የተሾመ ።
ወዘዲበ ፡ ገነት ፣
በገነት ፡ ባሉ ፡ ጻድቃን ፡ የተሾመ ፣
በገነት ፡ ያሉ ፡ ጻድቃንስ ፡ በእደ እግዚአብሔር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በእደ ፡ መልአክ ፡ አይጠበቁም ፡ ብሎ ፡ በገነት ፡ ባሉ ፡ ዕፀው ። አዕዋፍ ፡ የተሾመ ።
ወዘኪሩቤል ።
በኪሩቤል ፡ ላይ ፡ የተሾመ ። ሚካኤል ፡ በነገደ ፡ ሱራፌል ፡ እንደ ፡ ተሾመ ። ገብርኤልም ፡ የተሾመ ፡ በነገደ ፡ ኪሩቤል ፡ ነውና ።

፰ ። ወሖርኩ ፡ እስከ ፡ መካን ፡ ኀበ ፡ አልቦ ፡ ዘይትገበር ።
ሥራ ፡ ወደማይሠራበት ፡ ቦታ ድረስ ፡ ሄርኩ ።
ወርኢኩ ፡ በህየ፡ ግብረ ፡ ግሩመ ።
በዚያም ፡ የሚያስፈራ ፡ ሥራን ፡ አየሁ ፣
ኢሰማየ ፡ ልዑለ ፡ ወኢምድረ፡ ሡርርተ ፡ አላ ፡ መካነ ፡ በድው ፡ ዘድልው ፡ ወግሩም ።
ጽንዕተ ፡ ሲል ፡ ነው ። ምድረ፡በዳ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ሰማይ ፡ ወደታች ፡ ጽንዕት ፡ ምድር ፡ የለም ። ስነ ፡ ፍጥረት ነው ። አንድም ፡ መካነ ፡ ኃጥአን ፡ ነው ። ላገኛ ቸው ፡ መከራ ፡ ፍጹሜ ፡ እንደሌ ለው ፡ ለማጠየቅ ።

፱ ። ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ፯ተ ፡ ከዋክ ብተ ፡ ሰማይ ፡ እሡራን ፡ በላዕሌሁ ፡ ኅቡረ።
በዚያም ፡ ቦታ ፡ እንደ ፡ ታሳሳቅ፡ ተራሮች ፡ አንድ ፡ ሁነው ፡ በሱ የተጋዙ ፡ ሰባት ፡ የሰማይ ፡ ኮከቦ ችን ፡ አየሁ ። ደቂቀ ፡ ሴት፡ናቸው ።

በፍጹም : ተናግሮ : ሰባት : አለ ፤
ከዋክብት : አላቸው : በጥንተ :
ግብራቸው : ነው ፤
ከመ : አድባር : ዓበይት : ወከመ :
ዘእሳት : እንዘ : ይነድዱ ፤
እሳት : እንደ : ተያያዛቸው : እንደ :
ታላላቆች : ተራሮች : የሚነዱ :
ደቂቀ : ሴትን : ከዚያ : አንድነት :
ሁነው : አየሁ ፤
፲ ፤ ይእተ : ጊዜ : ዕቤ : በእንተ
ዓይ : ኃጢአት : ተአሥሩ ፤
ያን : ጊዜም : በምን : ኃጢአት :
ታሥረው : ተግዘዋል ?
ወበእንተ : ምንት : ዝየ : ተገድፉ ፤
በምንስ : ኃጢአታቸው : በዚህ
ወድቀዋል ? አልሁ ፤
፲፩ ፤ ወይቤለኒ : ዑርኤል : ፩ዱ :
እመላእክት : ቅዱሳን : ዘምስሌየ :
ውእቱ : ወይመርሐኒ ፤
ከእኔ : ጋራ : ያለ : ወደ : ወደደ
ውም : ሥራ : የሚመራኝ : ከከ
በሩ : ከመላእክት : አንዱ : ዑራኤ
ልም : እንዲህ : አለኝ ፤
ወይቤ : ሄኖክ : በእንተ : መኑ :
ትሴአል : ወበእንተ : መኑ : ትጤ
ይቅ : ወትጽሕቅ ፤
ሄኖክ : ስለማን : ትጠይቃለህ ?
ስለማንስ : ልትረዳ : ትተጋለህ ?
አለኝ ፤
እምከዋክብት : እለ : የኃልፉ : ትእ
ዛዘ : እግዚአብሔር ፤
ከደቂቀ : ሴት : አንድ : ሳይቀሩ :
በእግዚአብሔር : ትእዛዝ : የተ
ጋዙ ፤ አንድም : ትእዛዘ :
እግዚአብሔርን : ያለፉ : ናቸው ፤

፲፪ ፤ እሉ : እሙንቱ : መላእክት
እለ : ኃለፉ : ትእዛዘ : እግዚአብሔር
ልዑል ፤
እኒህ : ከፍ : ያለ : የእግዚአብሔርን
ትእዛዝ : ያፈረሱ : የሴት : ልጆች :
ናቸው ፤
ወተአሥሩ : በዝየ : እስከ : ይትፌጸም
ትእልፊተ : ዓለም : ኍልቈ : መዋዕለ
ኃጢአቶሙ ፤
የኃጢአታቸው : ዘመን : ቍጥር
የሚሆን : የዚህ : ዓለም :
ቍጥር : እስኪፈጸም : ድረስ :
ተግዘዋል ፤
፲፫ ፤ ወእምህየ : ሖርኩ : ካልዓ
መካነ : እምዝ : ዘይጌርም ፤
ከዚያም : ከዚህ : ቦታ : ወደሚያ
ስፈራ : ወደሌላ : ቦታ : ሔድኹ ፤
፲፬ ፤ ወርኢኩ : ግብረ : ግሩመ ፤
በዚያም : የሚያስፈራ : ሥራ :
አየሁ ፤
እሳት : ዓቢይ : በህየ : ዘይነድድ :
ወያንበለብል ፤
በዚያም : ቦታ : ፈጽሞ : የሚቃ
ጠል : ታላቅ : ቋያ : አለ ፤
ወሞሰርት : ቦቱ ፤
መጋዝ : አለበት ፤
ወወሰኑ : እስከ : ቀላይ : ፍጹም ፤
ጥርሱ : በምልዓት : ፍጹም :
እስከሆነ : እስከ : ውቅያኖስ :
ነው ፤ አንድም : ወሞሰርት :
ሰይፍ : አለ ፤ ወሰኑ : ጫፉ :
በምልዓት : ፍጹም : እስከ : ሆነ :
እስከ : ውቅያኖስ : ነው ፤

፲፫ ፡ አዕማደ ፡ እሳት ፡ ዓበይት ፡
ዘያወርድዎሙ ፡
ሥሳሴ ፡ መላእክት ፡ ወደሲኦል
ወደገሃነም ፡ የሚያወርዷቸው ፡
ደቂቀ ፡ ሴት፡ እሱበት ፡
ወኢአምጣኖ ፡
የወርዱን ፡ ቁመቱን ፡
ወኢዕበዮ ፡
ስፋቱን ፡
ኢክህልኩ ፡ ነጽሮ ፡
ማየት ፡ አልቻልኹም ፡
ወሰዕንኩ ፡ ነጽሮ ፡ ዓይኑ ፡
መልክዑ ፡ ሲል ፡ ነው ፡ መልኩ
ንም ፡ ማየት ፡ አልቻልኹም ፡ አን
ድም ፡ ወነጽሮ ፡ ማየት ፡ አልቻል
ኹም ፡ ዓይኑ ፡ ምንድር ፡ ነው ?
፲፬ ፡ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ እቤ ፡ እፎ ፡
ግሩም ፡ ዝንቱ ፡ መካን ፡ ወሕማም
ለነጽሮ ፡
ያን ፡ ጊዜም ፡ ይህ ፡ ቦታ ፡ እን
ዴት ፡ የሚያስፈራ ፡ ነው ፡ ሲያ
ዩትም ፡ ደዌ ፡ ነው ፡ አልኩ ፡
፲፭ ፡ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ አውሥአኒ
ዑርኤል ፡ ፩ዱ ፡ እመላእክት ፡ ቅዱሳን ፡
ዘምስሌየ ፡ ሀለወ ፡
ያን ፡ ጊዜም ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡
ከክበሩ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡
ዑራኤል ፡ መለሰልኝ ፡
፲፮ ፡ ወአውሥአኒ ፡ ወይቤለኒ ፡
ሄኖክ ፡ ምንት ፡ ውእቱ ፡ ፍርሃትከ ፡
ከመዝ ፡
ሄኖክ ፡ እንደዚህ ፡ አድርገህ ፡ መፍ
ራትህ ፡ ምንድር ፡ ነው?

ወድንጋጤከ ፡ በእንተዝ ፡ ግሩም ፡ መካን ፡
ወቅድመ ፡ ገጹ ፡ ለዝ ፡ ሕማም ፡
ስለዚህ ፡ ስለሚያስፈራው ፡ ቦታስ ?
በዚህ ፡ መከራ ፡ ፊት ፡ ይህን ፡
ያህል ፡ መደንገጥህ ፡ ለምንድር
ነው ?
፲፯ ፡ ወይቤለኒ ፡ ዝ ፡ መካን ፡
ቤተ ፡ ሞቅሖሙ ፡ ለመላእክት ፡ ወበህየ
ይትአኀዙ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፡
ይህም ፡ ቦታ ፡ ለደቂቀ ፡ ሴት ፡
የግዞት ፡ ቦታቸው ፡ ነው ፡ በዚ
ያም ፡ ቦታ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለም
ድረስ ፡ ይጋዛሉ ፡
[illegible] ፡ ወእምህየ ፡ ሖርኩ ፡ ካልዐ
መካነ ፡
ከዚያም ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ቦታ ፡
ሄድኹ ፡
ወአርአየኒ ፡ በምዕራብ ፡ ደብረ ፡ ዓቢየ
ወነዋኀ ፡
በምዕራብም ፡ ረጅምና ፡ ታላቅ፡
የሆነ ፡ ተራራን ፡ አሳየኝ ፡
ወኩኵሐ ፡ ጽኑዐ ፡
የጸና ፡ ዐለትንም ፡ አሳየኝ ፡
[illegible] ፡ ወ፬ቱ ፡ መካናት ፡ ሠናያት ፡
በአጠገቡ ፡ ያማማሩ ፡ አራት ፡
ቦታዎች ፡ አሉ ፡ ሠናያት ፡
መካነ ፡ ኃጥአንን ፡ በመካነ ፡ ጻድ
ቃን ፡ አስጠግቶ ፡ ሠናያት ፡ አለ ፡
ወበውስቴቱ ፡ ዘቦቱ ፡ ዕሙቅ ፡ ወር
ሒብ ፡
በውስጡ ፡ ስፊነት ፡ ጥልቅነት
አለ ፡ አንድም ፡ ወበውስቴቱ ፡
ወበጥቃሁ ፡ ሲል ፡ ነው ፡ በመ

ካን ፡ ጻድቃን ፡ አጠገብ ፡ ያለ ፡
መካነ ፡ ኃጥአን ፡ ዕሙቅ ፡ ጥልቅ፡
ነው ፡ ወርሒብ ፡ ሰፊ፡ ነው ።
ወልሙጽ ፡ ጥቀ ፡ ከመ ፡ ልሙጽ ፡
ዘያንኰረኵር ።
እንደልዝብ ፡ ደንጊያ ፡ የሚያዳ
ልጥ ፡ ነው ።
ወዕሙቅ ፡ ወጽልመት ፡ ለነጽሮ ።
ለማየት ፡ ጥልቅ ፡ ጨለማ ፡ ነው ።
[redacted] ። ውእተ ፡ ጊዜ ፡ አውሥአኒ
ሩፋኤል ፡ ፩ዱ ፡ እመላእክት ፡ ቅዱ
ሳን ፡ ዘሀለወ ፡ ምስሌየ ።
ያንጊዜም ፡ ከክቡሩ ፡ መላእክት
ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ፡ አንዱ፡ ሩፋ
ኤል ፡ መለሰልኝ ።
፫ ። ወይቤለኒ ፡ እላ ፡ መካናት ፡
ሠናያት ፡ ከመ ፡ ይትጋብኡ ፡ ዲቤሆን ፡
መናፍስቲሆሙ ፡ ለምውታን ፡ ሎሙ ፡
እሉንቱ ፡ ተፈጥሩ ።
ተፈጥራ ፡ ሲል ፡ ነው ። እላና ፡
እሉንቱ ፡ አንድ ፡ ወገን ። ተድላ ፡
ደስታ ፡ የተመላባቸው ፡ እኒህ ፡
ቦታዎች ፡ በምግባር ፡ በሃይማ
ኖት ፡ ፍጹማን ፡ የሆኑ ፡ ጻድቃን ፡
ይገቡባቸው ፡ ዘንድ ፡ ተፈጠሩላ
ቸው ።
ወዝየ ፡ ያስተጋብኡ ፡ ነፍሳተ ፡ ውሉደ
ሰብእ ።
ሥላሴ ። መላእክት ፡ የደጋግ ፡
ሰዎች ፡ ነፍሶችን ፡ ከዚህ ፡ ይሰበ
ስቡ ዘንድ ፡ ይሰበስባሉ ።
፬ ። ወእሉንተ ፡ መካናተ ፡ ኀቡ
ያንብርዎሙ ፡ ገብሩ ።
እነርሱ ፡ የሚያኖሩባቸውን ፡
ቦታዎች ፡ በኅው ፡ ቦታ ፡ ለጻድቃን ፡
እንደ ተፈጠረ ፡ ክፉውም ፡ ቦታ
ለኃጥአን ፡ ተፈጠረ ።
እስከ ፡ ዕለተ ፡ ኰነኔሆሙ ።
እስኪፈረድባቸው ።
ወእስከ ፡ አመ ፡ ዕድሜሆሙ ።
እስከ ፡ ዘመናቸው ፡ ድረስ ።
፭ ። ወዕድሜ ፡ ዓቢይ ፡ ውእቱ ።
ዘመኑም ፡ ብዙ ፡ ነውና ።
እስከ ፡ አመ ፡ ኰነኔ ፡ ዓቢይ ፡ በላዕ
ሌሆሙ ።
ፍጹም ፡ ፍርድ ፡ በእነርሱ ፡ ላይ ፡
እስኪደረግ ፡ ዘመኑም ፡ ብዙ ፡
ነው ።
፮ ። ወርኢኩ ፡ መናፍስተ ፡ ውሉደ ፡
ሰብእ ፡ እንዘ ፡ ምውታን ፡ ውእቶሙ ።
የደጋግ ፡ ሰዎች ፡ ልጆች ፡ ነፍሶ
ችንም ፡ አየሁ ።
ወእንዘ ፡ ምውታን ፡ ውእቶሙ ፡ ወቃ
ሎሙ ፡ ይበጽሕ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡
ወይሰኪ ።
የጻድቃን ፡ ነፍሶች ፡ ምውታን ፡
ሁነው ፡ ሳሉ ፡ ቃላቸው ፡ እስከ
ሰማይ ፡ ሲደርስ ፡ ኃጥአንን ፡
ሲከስ ፡ ሲያጣላ አየሁ ።
፯ ። ውእተ ፡ ጊዜ ፡ ተስእልክዎ ፡
ለሩፋኤል ፡ ዘሀሎ ፡ ምስሌየ ።
ያንጊዜም ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡
ሩፋኤልን ፡ ጠየቅሁት
ወእቤሎ ፡ ዝ ፡ መንፈስ ፡ ዘመኑ ፡
ውእቱ ።

ይህ ፡ የማን ፡ ነፍስ ፡ ነው? አልኩት ፤

ዘከመዝ ፡ ቃሉ ፡ ይበጽሕ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ ወይሰኪ ፤

ቃሉ ፡ እስከ ፡ ሰማይ ፡ የሚደርስ ፣ የሚከስ ፣ የሚያጣላ ፡ የማን ፡ነፍስ ፡ ነው ? አልኩት ፤

፰ ፤ ወአውሥአኒ ፡ ወይቤለኒ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ዝንቱ ፡ መንፈስ ፡ ውእቱ ፡ ዘይወጽእ ፡ እምአቤል ዘቀተሎ ፡ ቃየል ፡ እኁሁ ፤

ይህ ፡ ነፍስ ፣ ወንድሙ ፡ ቃየል በግፍ ፡ ከገደለው ፡ ከአቤል ፡ የተለየ ፡ ነፍስ ፡ ነው ፡ አለኝ ፤

ወይሰኪ ፡ ኪያሁ ፡ እስከ ፡ አመ ፡ ይትኀጐል ፡ ዘርዑ ፡ እምገጸ ፡ ምድር ፤

ልጁ ፡ (ዘሩ) ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ እስኪ ፡ ጠፋ ፡ ድረስ ፤

ወእምዘርአ ፡ ሰብእ ፡ ይማስን ፡ ዘርዑ ፤

ልጁ ፡ ዘሩ ፡ ከሰው ፡ ልጅ ፡ ተለይቶ ፡ እስኪጠፋ ፡ድረስ ፡ ነው ፤

፱ ፤ ወውእተ ፡ ጊዜ ፡ ተስእልክዎ በእንቲአሁ ፤

በቃየል ፡የሚፈረድበትን ፤

ወበእንተ ፡ ኩነኔ ፡ ኵሉ ፤

በኃጥአን ፡ የሚፈረድባቸውን ፤ አንድም ፡ ለአቤል ፡ የሚፈረድለትን ፤ አንድም ፡ ለጻድቃን ፡ የሚፈረድላቸውን ፡ ጠየቅሁት ፤

ወእቤ ፡ በእንተ ፡ ምንት ፡ ተፈልጠ ፡ ፩ዱ ፡ እም፩ዱ ፤

የጻድቃን ፡ ቦታ ፡ ከኃጥአን ፤ የኃጥአን ፡ ቦታ ፡ ከጻድቃን ፡ ስለምን ፡ ተለየ ? ብዬ ፡ ጠየቅሁት ፡፡

፲ ፤ ወአውሥአኒ ፡ ወይቤለኒ ፡ እሉንቱ ፡ ፫ቱ ፡ ተገብሩ ፡ ከመ ፡ ይፍልጡ ፡ መንፈሰሙ ፡ ለሙታን ፤

የጻድቃንን ፡ ነፍስ ፡ ከኃጥአን ፡ ይለዩ ፡ ዘንድ ፡ እነዚህ ፡ ሦስቱ ቦታዎች ፡ ተፈጠሩ ፤

ወከመዝ ፡ ተፈልጠ ፡ መንፈሶሙ ፡ ለጻድቃን ፤

የጻድቃን ፡ ቦታቸው ፡ እንደ ፡ ተለየ ፡ ነፍሳቸውም ፡ ተለየ ፤

ዝውእቱ ፡ ነቅዓ ፡ ማይ ፡ ዘበላዕሌሁ ብርሃን ፤

ብርሃን ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ያለበት ነቅዓ ፡ ማይ ፡ የውኃ ፡ ምንጭ ፤ ይህ ፡ ነው ፤ አንድም ፡ ብርሃን ጌታ ፡ ያደረበት ፡ የክብር ፡ የልጅነት ፡ ቦታ ፡ ይህ ፡ ነው ፤

፲፩ ፤ በከመ ፡ ከማሁ ፡ ተፈጥረ ፡ ለኃጥአን ፡ ሶበ ፡ ይመውቱ ፡ ወይትቀበሩ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፤

አሁን ፡ እንደተናገርሁት ፡ ለጻድቃን ፡ በጎው ፡ ቦታ ፡ እንደተፈጠረ፡ ለኃጥአንም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሙተው ፡ በተቀበሩ ፡ ጊዜ ፡ ሊኖሩበት ፡ ክፉው ፡ ቦታ ፡ ተፈጠረ ፤

፲፪ ፤ ወኮነኔ ፡ ኢኮነ ፡ በላዕሌሆሙ ፡ በሕይወቶሙ ፤

በሕይወት ፡ ሳሉ ፡ አልተፈረደባቸውም ፡ ነበረና ፤

፲፫ ፤ ወበዝየ፡ ይትፈለጣ ፡ ነፍሳቲሆሙ ፡ ዲበ ፡ ዛቲ ፡ ዓባይ ፡ ዓፅር ፡ እስከ ፡ አመ ፡ ዓባይ ፡ ዕለት ፡ እንተ፡ ኵነኔ፤

እስከ ፡ ዕለተ ፡ ምጽአት ፡ ድረስ ይህችን ፡ ጭንቅ ፡ መከራ ፡ ሊቀበሉ ፡ ኃጥአን ፡ ከጻድቃን ፡ በዚህ ፡ ቦታ ፡ ይለያሉ ።

ወመቅሠፍት ፡ ወፃዕር ፡ ለእለ ፡ ይረግሙ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፡ ወበቀል ለነፍሶሙ ።

እግዚአብሔርን ፡ ለሚክዱ ፤ ሰውን ፡ ለሚሳደቡ ፤ ይህች ፡ ጭንቅ ፡ መከራ ፡ ለዘለዓለሙ ። አለችባቸው ። ለነፍሳቸውም ፡ በቀል ፡ አለባት ።

፲፩ ። ወበህየ ፡ የአሥሮሙ ፡ እስከ ለዓለም ፡ ወእመኒ ፡ ውእቱ ፡ እምቅድመ ፡ ዓለም ፡

ምንም ፡ እንኳ ፡ ከዓለም ፡ ጀምሮ ፡ ቢሆን ፡ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ አሥሮ ፡ ያግዛቸዋል ። ዓለም ፡ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ ለኃጥአን ፤ ዓቢይ ፡ ዓለም ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ ለጻድቃን ፡ ከመሰጠቱ ፡ አስቀድሞ ፡ ቢሆን ፡ በዚህ ፡ ይታሠራሉ ።

፲፪ ። ወከመዝ ፡ ተፈልጠ ፡ ለነፍሰሙ ፡ ለእለ ፡ ይሰክዩ ፡ ወእለ ፡ ያሬእዩ ፡ በእንተ ፡ ኅጕለት ፡ እመ ፡ ተቀትሉ በመዋዕለ ፡ ኃጥአን ።

የኃጥአን ፡ ቦታ ፡ እንደተለየ ፡ በኃጥአን ፡ ወራት ፡ በሞቱ ፡ ጊዜ ፡ የጥፋታቸውን ፡ ነገር ፡ የሚያሳዩ ፡ ኃጥአንን ፡ ለሚከሱ ፤ እግዚአብሔርን ፡ ለሚለምኑ ፡ ለጻድቃን ፡ ነፍስ ፡ ቦታ ፡ ተለየ ።

[redacted] ፤ ወከመዝ ፡ ተፈጥሩ ፡ ለነፍሰሙ ፡ ለሰብእ ፡ እኩያን ፡ እለ ፡ ኢኮኑ ፡ ጻድቃን ፡ አላ ፡ ኃጥአን ፡ እለ ፡ ፍጹማን ፡ አበሳ ።

በኃጢአት ፡ ፍጹማን ፡ የሆኑ ፤ ኃጥአንን ፡ እንጂ ፡ ጻድቃን ፡ ላይደሉ ። የክፉዎች ፡ ሰዎች ፡ ነፍስም ። ለጻድቃን ፡ እንደተለየ ፡ ቦታ ፡ ተለየ ።

ወምስለ ፡ አባሲያን ፡ ይከውኑ ፡ ከማሆሙ ።

እኩሌቶቹ ። ኃጥአን ፡ እንደ ፡ እኩሌቶቹ ፡ ኃጥአን ፡ ይሆናሉ ። አንድም ፡ እኩሌቶቹ ፡ ኃጥአን ፡ ከእኩሌቶቹ ። ኃጥአን ፡ ጋራ ፡ ይፈረድባቸዋል ። አንድም ። ኃጥአን ፡ ከአጋንንት ፡ ጋራ ። ይፈረድባቸዋል ።

፲፫ ። ወነፍሶሙሰ ። ኢትትቀተል ፡ በዕለተ ፡ ኰነኔ ።

በፍርድ ቀን ። መከራ ፡ ስትቀበል ፡ ትኖራለች ፡ እንጂ ፡ ነፍሳቸው ፡ ግን ፡ አትሞትም ። አንድም ፡ ሰውነታቸው ፡ ሳትነሣ ። ፈርሳ ፡ በስብሳ ። አትቀርም ።

ወኢይትነሥኡ ፡ እምዝየ ።

ትዋኤያቸው ፡ ዘለኃሣር ፡ ስለሆነ ። ኢይትነሥኡ ፡ አለ ። አንድም ፡ ከገሃነም ፡ አይወጡም ።

፲፬ ። ውእተ ፡ ጊዜ ፡ ባረክዎ ፡ ለእግዚእ ፡ ስብሐት ።

ያን ፡ ጊዜም ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታዬን ፡ አመሰገንሁት ።

ወእቤ ፡ ቡሩክ ፡ ውእቱ ፡ እግዚእየ ፡ እግዚእ ፡ ስብሐት ፤ ወጽድቅ ፤ ዘኰሉ ፡ ይመልክ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።

እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ድረስ ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ የክብርና ፡ የጽድቅ ፡ ጌታዬም ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ፡ አልሁ ።

ወጽድቅ : ቢል ፣ ፈታሒ : በጽድቅ ፡ ጌታዬ : ቡሩክ : ነው : አልሁ ፤

፵፱ ፤ ወእምህየ ፡ ሖርኩ : ካልአ : መካነ : መንገለ : ዓረብ : እስከ : አጽናፈ : ምድር ፤
ከዚያም : እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ድረስ : በምዕራብ : ወዳለ : ወደሌላ : ቦታ :ሄድኹ ፤

[illegible] ፤ ወርኢኩ : እሳተ : ዘይነድድ : ወይረውፅ : እንዘ ፡ ኢያዐርፍ ፤
ሳያርፍ : እየሮጠ : የሚነድድ : እሳትንም : አየሁ : ፀሐይን : ነው ፤
ወኢይነትግ : እምሩፀቱ : መዓልተ : ወሌሊተ ፤
በመዓልትም ፡ በሌሊትም ፡ ከመሄዱ ፡ ሳያቋርጥ ፡ ሳያርፍ : አየሁ ፤
አላ ፡ ከማሁ : ክመ ፤
በመዓልትም : በሌሊትም : መቸም: መቸ : ይሄዳል : እንጂ ፤

፶፩ ፤ ወተስዕልኩ : እንዘ : እብል : ዝንቱ : ምንት : ውእቱ : ዘአልቦ ዕረፍት ፤
ይህ ፡ ዕረፍት ፡ የሌለው : ምንድነው ? ብዬ ፡ ጠየቅሁ ፤

፶፪ ፤ ውእተ : ጊዜ : አውሥአኒ ራጉኤል: ፩ዱ : እመላእክት : ቅዱሳን ዘሀሉ : ምስሌየ ፤
ያን: ጊዜ : ከእኔ : ጋራ : ያለ : ከከበሩ : ከመላእክት : አንዱ : ራጉኤል : መለሰልኝ ፤

ወይቤለኒ : ዝንቱ : ዘርኢከ : ሩጸቶ : ዘመንገለ ፡ ዓረብ ፡ እሳት : ዘይነድድ፤
ወደምዕራብ ፡ ሲኼድ : ያየኸው የሚያበራ : ይህ ፡ እሳት ፤
ውእቱ : ኵሉ : ብርሃናተ : ሰማይ ፤
ይኸውም : ፀሐይ : ጨረቃ : ከዋክብት : ናቸው ፤ አንዱን : ፀሐይን : ከጠየቀ ፡ ዘንድ : ከዚህ : አያይዞ : ሁሉንም ፡ ነገረው ፡፡

## ምዕራፍ ፸፫ ፤
## ጉባኤ

፩ ፤ ወእምህየ : ሖርኩ : ካልአ ፡ መካነ : ምድር ፤
ይህን ፡ ራእይ : ካየሁበት : ወደሌላ: ቦታ : ሄድኹ : አለ ፤

[illegible] ፤ ወአርአየኒ : ደብረ : እሳት : ዘያንበለብል ፡ መዓልተ ፡ ወሌሊተ ፤
በመዓልትም : በሌሊትም : የሚያበራ : የዕንቍ : ተራራ ፡ አየሁ፤
አንድም፡ የሚያበራ : ዕንቍ ፡ ያለበትን : ተራራ : አየሁ ፤

[illegible] ፤ ወሖርኩ ፡ መንገሌሁ ፡ ወርኢኩ ፯ተ : አድባረ : ክቡራን ፤
የከበሩ : ሰባት : የዕንቍ : ተራሮችን ፤ አንድም : ዕንቍ : ያለባቸው : ተራሮችን : አየሁ፤

፫ ፤ ወኵሉ : ፩ዱ : እምነ : ፩ዱ: እንዘ : ይትዌለጥ ፤
አንዱ : ካንዱ : በመልክም : በብርሃንም ፡ ይለወጣል ፤

ወአዕባነ ፡ ክቡራነ ። ወሠናያነ ።
ያማሩና ፡ የከበሩ ፡ ድንጋዮችንም፡
አየሁ ።
ወኵሉ ፡ ክቡር ።
ሁሉም ፡ ጽሩያን ፡ ናቸው።
፬ ። ወስቡሕ ፡ ራእዮሙ ።
መልካቸው ፡ የበራ ፡ ብሩህ ፡ ነው ።
ወሠናይ ፡ ገጸሙ ።
አካላቸው ፡ ጽሩይ ፡ ነው ። ፊታቸ
ውም ፡ ያማረ ፡ ነው ።
ወሠለስቱ ፡ መንገለ ፡ ጽባሕ ።
ሦስቱ ፡ በምሥራቅ ፡ ናቸው ።
ወጽኑዓን ፡ ፩ዱ ፡ ዲበ ፡ ፩ዱ ።
አንዱን ፡ ካየሁት ፡ በኋላ ፡ ያየ
ሁት ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ ጽኑ
ዓን ፡ ናቸው ። አንድም ፡ ጽው
ናን ፡ ቢል ፡ አንዱ ፡ ከአንዱ ፡ ጋራ፡
የተያያዙ ፡ የተደራረቡ ፡ ናቸው ።
፭ ። ወሠለስቱ ፡ መንገለ ፡ ሰሜን ፡
፩ዱ ፡ ዲበ ፡ ፩ዱ ፡ ጽኑዓን ።
ሦስቱም ፡ በሰሜን ፡ በኩል ፡ ናቸው ፡
አንዱን፡ ካየሁ ፡ በኋላ ፡ ያየሁት ፡
አንዱም ፡ አንዱም ፡ ጽኑዓን ፡
ናቸው ። አንድም፡ ጽውናን ፡ ቢል፡
አንዱ ፡ ከአንዱ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡
ጣት ፡ የተያያዙ ፡ ናቸው ።
ወቈላት ፡ ዕሙቃት ፡ ወጠዋያት ።
ጠማማ ፡ ጥልቅ ፡ የሆኑ ፡ ቈላዎች ፡
አሉ ፡ አለ ። በኃጢአት ፡ በክህደት ፡
ፍጹማን ፡ የሆኑ ፡ የሚኖሩባት ፡
ብሔረ ፡ አሕዛብ ፡ አለ ።
አሐቲ ፡ ለአሐቲ ፡ ኢይትቃረባ ።
አሐቲ፡ ወአሐቲ ፡ እንደማለት ።
አንዲቱና ፡ አንዲቱ ፡ አይቀራረ
ቡም ። አንድም ፡ ኢትቀርባ ፡ ቢል ፡
አንዲቱ ፡ አንዲቱን ፡ አትቀርባ
ትም ። አሕዛብ ፡ በግብርም ፡ በኃጢ
አትም ፡ አይቀራረቡም ። ሥራ
ቸው ፡ ልዩ ፡ ልዩ፡ ነውና ።
፮ ። ወሳብዕ ፡ ደብር ፡ ማእከሎሙ
ለእሉንቱ ።
በመካከላቸው ፯ተኛ ፡ ተራራ ፡
አለ ።
ወኑኀሙስ ፡ ይትማሰሉ ፡ ኮሎሙ ፡
ከመ ፡ መንበረ ፡ አትራኖስ ።
ቁመታቸውም፡ እንደ ፡ አፍርንጂ ፡
ወምበር ፡ የተካከለ ፡ የተመሳሰለ ፡
ነው ። ለጊዜው ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡
አሳይቶታል ። ለኋላው ፡ ምሳሌ ፡
ነው ። መጀመሪያ ፡ ያየው ፡ ተራራ ።
ገነት ፡ ናት ። በዚያ ፡ ያሉ ፡ አዳ
ምና ፡ሔዋን ፡ ናቸው ። ሁለተኛ ፡
ያየው ፡ ተራራ ፡ ደብር ፡ ቅዱስ ፡
ነው ። በዚያም ፡ ያሉ ፡ ደቂቀ ፡
ሴት ፡ ናቸው ። ሦስተኛ ፡ ያየው ፡
ተራራ ፡ ሐመረ ፡ ኖኅ ፡ ናት ።
በዚያ ፡ ያሉት ፡ ኖኅ ፡ ከነልጆቹ ፡
ናቸው ። አራተኛ ፡ ያየው ፡
ተራራ ፡ ደብረ ፡ ሲና ፡ ነው ።
በዚያ ፡ ያሉ ፡ ሙሴ ፡ አሮን ፡
ናቸው ። አምስተኛ፡ ያየው ፡
ደብረ ፡ ዘይት ፡ ነው ። በዚያ ፡
ያሉ ፡ ዳዊት ፡ ሰሎሞን ፡ ናቸው ።

ስድስተኛ ፡ ያየው ፡ ደብረ ፡ ታቦር ፡ ነው ፤ በዚያ ፡ ያሉ ፡ ባርቅ ፡ ዲቦራ ፡ ናቸው ፤ ሰባተኛ ፡ ያየው ፡ ቀራንዮ ፡ ነው ፤ በዚያ ፡ ያሉ ፡ ጌታ ፡ ሐዋርያት ፡ ናቸው ፤ ሳብዕ ፡ ያለው ፡ ደብረ ፡ ሲና ፡ ነው ፤ አሁን ፡ ሰተራራው ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፤ ማእከል ፡ አለው ፤ በምሥራቅ ፡ ያሉ ፡ ገነት ፤ ደብር ፡ ቅዱስ ፤ ሐመረ ፡ ኖኅ ፡ ናቸው ፤ በምዕራብ ፡ ያሉ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፤ ደብረ ፡ ታቦር ፤ ቀራንዮ ፤ ናቸው ፤ መካከሉ ፡ ደብረ ፡ ሲና ፡ ነው ፤

፲ ፤ ወየዐውድዎ ፡ ዕፀው ፡ መዓዛ ፤

መዓዛ ፡ ያላቸው ፡ እንጨቶች ፡ ከበውታል ፤ ማለት ፡ ሕገጋቱ ፡ ከበውታል ፤

ወሀሎ ፡ ውስቴቶሙ ፡ ዕፅ ፡ አልቦ ፡ ግሙራ ፡ እመ ፡ ፄነወኒ ፡ ወኢአሐዱ እምውስቴቶሙ ፤

በመካከላቸውም ፡ አንድ ፡ እንጨት ፡ አለ ፤ በሽተተኝም ፡ ጊዜ ፡ ከእነርሳቸው ፡ አንዱ ፡ ስንኳ ፡ እንደ ፡ እርሱ ፡ የሸተተኝ ፡ የለም ፤ አንድም ፡ ኢታምልክ ፡ በመካከላቸው ፡ አለ ፤ ከሕግጋቱም ፡ ሁሉ ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ በመስጠት ፡ ኢታምልክን ፡ የሚመስለው ፡ የለም ፡፡

፫ ፤ ወባዕዳንሂ ፡ ዘከማሁ ፡ ኢኮነ ፡ ዘይምዕዝ እምኩሉ ፡ መዓዛ ፤

ኢኮነም ፡ ካለ ፡ ባዕድሂ ፤ ባዕዳንሂም ፡ ካለ ፡ ኢኮኑ ፡ ባለ ፡ በቀና ፡ ነበር ፤ በሽተተኝ ፡ ጊዜ መዓዛ ፡ ካላቸው ፡ ዕፀው ፡ እንደ እርሱ ፡ የሚሸት ፡ የለም ፤ ማለት ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ ካላቸው ፡ ሕገጋት ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ በማስጠት ፡ እንደ ፡ ኢታምልክ ፡ ያለ ፡ የለም ፤

፬ ፤ ወቈጽሉሂ ፡ ወጽጌሁ ፤ ወዕፁ ፡ ኢይጸመሂ ፡ ለዓለም ፤

ቅጠሉ ፤ አበባው ፤ እንጨቱ ፤ ለዘለዓለም ፡ አይጠወልግም ፤ ማለት ፡ በኢታምልክ ፡ የሚገኘው ፡ ጸጋ ፤ ክብር ፤ አይጠፋም ፤ ማለት ፡ ነው ፤

፲ ፤ ወፍሬሁኒ ፡ ሠናይ ፤

ፍሬውም ፡ ብዙ ፡ ነው ፤

ወፍሬሁሰ ፡ ከመ ፡ አስካለ ፡ በቀልት ፤ ፍሬውም ፡ እንደ ፡ ዘንባባ ፡ ፍሬ ፡ ንብብር ፡ ነው ፤ ማለት ፡ በኢታምልክ ፡ የሚገኘው ፡ ክብር ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ በፊት ፡ ለማየት ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነው ፤ ማለት ፡ ኢታምልክ ፡ በዓይነ ፡ ልቡና ፡ ለማየት ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነው ፤

፲፩ ፤ ወውእተ ፡ ጊዜ ፡ ዕቤ ፡ ነዋ ፡ ዝንቱ ፡ ሠናይ ፡ ዕፅ ፡ ወሠናይ ፡ ለርእይ ፡ ወአዳም ፡ ቈጽሉ ፡ ወፍሬሁኒ ፡ ሞገስ ፡ ጥቀ ፡ ለርእየ ፡ ገጽ ፤

ያን ፡ ጊዜም ፡ ይህ ፡ እንጨት ፡ እነሆ ፡ ያማረ ፡ ነው ፤ ቅጠሉ ፡ ጽፍቅ ፡ ነው ፤ ፍሬው ፡ ንብብር ፡ ሊያዩትም ፡ ፈጽሞ ፡ የተወደደ ነው ፡ አልሁ ፤

፲፪ ፤ ወውእተ ፡ ጊዜ ፡ አውሥአኒ ፤ ሚካኤል ፡ አሐዱ ፡ እመላእክት ፡

ቅዱሳን ፡ ወክቡራን ፡ ዘምስሌየ ፡ ሀሉ ወውእቱ ፡ ዘዲቤሆሙ ፡
ያን ፡ ጊዜ ፡ ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ በላያቸው ፡ የተሾመ ፡ ከሊቃን ፡ መላእክት ፡ አንዱ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ መለሰልኝ ፡

፲፫ ፡ ወይቤለኒ ፡ ሄኖክ ፡ ምንተ ፡ ትሴአል ፡ በእንተ ፡ መዓዛሁ ፡ ለዝ ፡ ዕፅ ፡ ወትጤይቅ ፡ ከመ ፡ ታእምር፡
ሄኖክ ፡ የዚህን ፡ የእንጨት ፡ ሽታ ፡ ነገር ፡ ለምን ፡ ትጠይቃለህ? ልታውቅስ ፡ ለምን ፡ ትመረምራለህ? አለኝ ፡ ማለት ፡ የዚህን ፡ የኢታምልክን ፡ ነገር ፡ ልታወቅ ትወዳለህ ? አለኝ፡

፲፬ ፡ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ አውሣእክዎ ፡ አነ ፡ ሄኖክ ፡ እንዘ ፡ እብል ፡ በእንተ ኵሉ ፡ እፈቅድ ፡ አእምር ፡ ወፈድፋደሰ ፡ በእንተዝ ፡ ዕፅ ፡
ያን ፡ ጊዜ ፡ እኔ ፡ ሄኖክ ፡ እንዲህ ፡ ብዬ ፡ መለስኩለት ፡ ማወቅስ ፡ የዕፀውን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፡ ይልቁንም ፡ የዚህን ፡ የዕፅ ፡ ነገር ፡ ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፡ ማለት ፡ ማወቅስ ፡ የሕገጋቱን ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፡ ይልቁንም ፡ የኢታምልክን ፡ ነገር ፡ ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፡

፲፭ ፡ ወአውሥአኒ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ ዝንቱ ፡ ደብር ፡ ዘርኢከ ፡ ነዋህ ፡ ዘርእሱ ፡ ይመስል ፡ መንበር፡ ለእግዚእ ፡ መንበሩ ፡ ውእቱ ፡ ኀበ ፡ ይነብር ፡ ቅዱስ ፡ ወዓቢይ ፡ እግዚእ ፡ ስብሐት፡ ንጉሥ ፡ ዘለዓለም ፡ ሶበ ፡ ይወርድ ፡ የሐውጻ ፡ ለምድር ፡ በሠናይ ፡
እርሱም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ መለሰልኝ ፡ ራሱ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ዙፋን ፡ የሚመስል ፡ ልዑል ፡ ሁኖ ፡ ያየኸው ፡ ይህችን ፡ ዓለም ፡ በበጎ ፡ ነገር ሊጐበኝ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ የሚቀመጥበት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ዙፋን ፡ ነው ፡ ማለት ፡ ራሱ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ዙፋን ፡ የሚመስል ፡ ልዑል ፡ ሁኖ ፡ ያየኸው ፡በበጎ ፡ ነገር ፡ በዘፈቀደ ተገልጾ ፡ ሕግ ፡ ሠርቶ ፡በተገለጸ ጊዜ ፡ የሚቀመጥባት ፡ ደብረ ፡ ሲና ፡ ናት ፡

፲፮ ፡ ወዝንቱኒ ፡ ዕፀ ፡ መዓዛ ፡ ሠናይ ፡ ወኢ፩ዱ ፡ ዘሥጋ ፡ አልቦ ፡ ሥልጣን ከመ ፡ ይግሥሦ ፡
ለዝንቱኒ ፡ ሲል ፡ ነው ፡ ይህንንም ፡ ዕፅ ፡ ከሥጋዊ ፡ ከደማዊ ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ ይነካው ፡ ዘንድ ፡ ሥልጣን ፡ የለውም ፡ ማለት ፡
እስከ ፡ አመ ዓቢይ ፡ ኵነኔ ፡ አመ ፡ ይትቤቀል ፡ ኵሉ ፡ ወይትፈጸም ፡ እስከ ፡ ለዓለም፡
ፍጹም ፡ ፍዳ ፡ በኃጥአን ፡ ፍጹም ፡ ክብር ፡ በጻድቃን ፡ በተፈጸመ ፡ ጊዜ ፡ ኃጥአንን ፡ በተበቀለ ፡ ጊዜ ፡ ፍጹም ፡ ቍርጥ ፡ ፍርድ ፡ እስኪደርስ ፡ ይነካው ፡ ዘንድ ፡ ሥልጣን ፡ የለውም ፡ በዘመነ ፡ ብሉይ ፡

እለ ፡ ጲሩጳይዳን ፡ እለ ፡ አንጥ
ያኮስ ፤ በዘመን ፡ ሐዲስ ፡ እለ ፡
መክስምያኖስ ፡ እለ ፡ ዲዮቅል
ጥያኖስ ፡ ተነሡ ፤ አላጠፋትም ፤

፲፫ ፤ ዝኩ ፡ ለጻድቃን ፡ ወለትሑ
ታን ፡ ይትወሀብ ፡ እምፍሬ ፡ ዚአሁ ፤
ከፍሬው ፡ ትሑታን ፡ ለሆኑ ፡
ለጻድቃን ፡ ይሰጣል ፤ ማለት ፡
በኢታምልክ ፡ የሚገኘው ፡ ክብር ፡
ለጻድቃን ፡ ይሰጣል ፤

ወይትወሀብ ፡ ለኅሩያን ፡ ሕይወት ፡
በምግባር ፡ በሃይማኖት ፡ ለተመ
ረጡ ፡ በኢታምልክ ፡ የሚገኘው
ክብር ፡ ይሰጣል ፤

፲፬ ፤ መንገለ ፡ መስዕ ፡ ይተከል ፡
ውስተ ፡ መካን ፡ ቅዱስ ፡ መንገለ፡
ቤቱ ፡ ለእግዚእ ፡ ንጉሥ ፡ ዘለዓለም ፤
የዘላለም ፡ ንጉሥ ፡ ወደሚሆን፡
በደጊቱ ፡ ማደሪያ ፡ በዘላለማዊው ፡
ንጉሥ ፡ በጌታ ፡ ቤት ፡ አንፃር ፡
በመስዕ ፡ በኩል ፡ በቅዱስ ፡ ቦታ፡
ባለ ፡ በከቡር ቦታ ፡ ይተካከላል ፤
በመካን ፡ ቅዱስ ፡ ደብረ ፡ ሲና፡
መንገለ ፡ መስዕ ፤ ደብረ ፡ ሲና ፡
በመስዕ በኩል ፡ ነውና ፡ መንገለ ፡
ቤቱ ፡ እለ ፤ ደብረ ፡ ሲና ፡ በቤተ፡
መቅደስ ፡ አንፃር ፡ ነውና ፤ ይህን፡
በበሉ ፡ ጊዜ ፤

፲፭ ፤ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ ይትፌሥሑ ፡
በፍሥሓ ፡ ወይትሐሠዩ ፤
ያን ፡ ጊዜ ፡ ፊጽመው ፡ ደስ ፡
ይላቸዋል ፤

፳ ፤ ውስተ ፡ ቅዱስ ፡ ያበውኡ ፡
ሉቱ ፡ መዓዛ ፡ በበአዕፅምቲሆሙ ፤
በየወገናቸው ፡ ወደ ፡ ስበረ ፡ ቦታ ፡
ሽቱን ፡ ያቀርቡለታል ፤

ወሕይወተ ፡ ብዙኀ ፡ የሐይዉ ፡ በዲበ
ምድር ፡ በከመ ፡ ሐይዉ ፡ አበዊከ፤
አባቶችህ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ እን
ደኖሩ ፤ እነሱም ፡ በዚህ ፡ ዓለም፡
ብዙ ፡ ዘመን ፡ ይኖራሉ ፤ ደስ ፡
ይላቸዋል ፤ ማለት ፡ ኢታምልክን ፡
ባወቁ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፤
ዕፀው ፡ ሁሉ ፡ መዓዛ ፡ ያቀርቡ
ለታል ፡ ማለት ፡ እሥራኤል ፡ ሁሉ፡
ኢታምልክን ፡ ያከብሩታል ፤ ያገ
ኙታል ፤ ቀድሞ ፡ ይህን ፡ የበሉ ፡
ሰዎች ፡ በሕይወት ፡ እንደኖሩ ፤
እንግዲህም ፡ ከዚህ ፡ ዕፅ ፡ የበሉ ፡
ሰዎች ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ፤
ማለት ፡ ኢታምልክን ፡ በሕገ ፡
ልቡና ፡ አምነው ፡ የኖሩ ፡ ሰዎች፡
በሕይወት ፡ እንዲኖሩ ፤ ኋላም ፤
የተነሡ ፡ ሰዎች ፡ ኢታምልክን ፡
እየጠበቁ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ፤
ይህን ፡ በሚበሉበት ፡ ዘመን ፡
ሕማም ፡ መከራ ፡ የለባቸውም፤
ማለት ፡ ኢታምልክን ፡ በሚጠ
ብቁበት ፡ ዘመን ፡ ሕማመ ፡ ሥጋ ፤
ሕማመ ፡ ነፍስ ፤ ኀዘነ ፡ ሥጋ ፡
ኀዘነ ፡ ነፍስ ፤ ድካመ ፡ ሥጋ ፡
ድካመ ፡ ነፍስ ፡ የለባቸውም ፤

[redacted] ፤ ወበመዋዕሊሆሙ ፡ ኀዘን ፡
ወሕማም ፡ ወጻማ ፡ ወመቅሠፍት ፡
ኢይገሥሦሙ ፤

በዘመናቸው ፡ መከራና ፡ ኃዘን ፤ መቅሠፍትና ፡ ድካምም አያገኛ ቸውም፤ (አይዳስሳቸውም) ፤
፳፱ ፤ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ ባረክዎ ፡ ለእግዚእ ፡ ስብሐት ፡ ንጉሥ ፡ ዘለ ዓለም ፤
እንደዚህም ፡ አድርጎ ፡ ፈጥሮ ፡ ሰጥ ቷቸዋልና ፡ የዘለዓለም ፡ ንጉሥ ፡ የሚሆን ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታን ፡ አመሰገንሁት አለ ፤
እስመ ፡ አስተዳለወ ፡ ከመዝ ለሰብእ ጻድቃን ወከመዝ ፡ ፈጠረ ፤
እንዲህ ፡ አድርጎ ፡ ወዳጆቹ ፡ ስለሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ኢታምልክን ፡ አዘጋጅቷልና ፤
ወይቤ ፡ የሀብዎሙ ፤
ይህን ፡ ዕፅ ፡ ይሰጧቸው ፡ ዘንድ ፡ አሏልና ፤ ማለት ፡ በኢታምልክ ፡ የሚገኘውን ፡ ሥርዓት ፡ ያስተም ሯቸው ፡ ዘንድ ፡ አስተምሯቸው ፡ ብሎ ፡ አሏልና ፡ አመሰገንሁት ፤
እንድም ፡ ሳብዕ ፡ ደብር ፡ ቀራን ዮን ፡ ማዕከል ፡ አለው ፤ በም ሥራቅ ፡ ያሉ ፡ ገነት ፤ ደብር ፡ ቅዱስ ፤ ሐመሬ ፡ ኖኅ ፡ ናቸው ፤ ወደ ፡ ምዕራብ ፡ ያሉ ፡ ደብረ ፡ ሲና ፤ ደብረ ፡ ዘይት ፤ ደብረ ፡ ታቦር ፡ ናቸው ፤ መዓዛ ፡ ያላቸው ፡ ዕፀው ፡ ከበውታል ፡ ማለት ፡ የጻድቃን ፡ የሰማዕታት ፡ መከራ ፡ ከበውታል ፤ መከራ ፡ የሚቀበሉ ፡ ጌታን ፡ አብነት ፡ እያደረጉ ፡ ነውና ፤ በውስጣቸው ፡ ከእርሳቸው ፡ መዓዛ ፡ የሚበልጥ ፡ ዕፅ ፡ አለ ፡ ማለት ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ በማስጠት ፡ ከሰማዕታት ፡ የሚበ ልጥ ፡ የጌታ ፡ መስቀል ፡ አለ ፤ በሸተተ ፡ ጊዜ ፡ በመዓዛ ፡ የሚመ ስለው ፡ የለም ፡ ማለት ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ በማስጠት ፡ የሚመስ ለው ፡ የለም ፤ ጻድቃን ፡ ሰማዕ ታት ፡ እንከበርበት ፡ ብለው ፡ ነው ፤ እሱ ፡ ማን ፡ አከብር ፡ አይል ፡ ክቡር ፤ አጸድቅ ፡ አይል ፡ ጻድቅ ፡ ነውና ፤ ቅጠሉ ፤ አበ ባው ፤ እንጨቱ ፡ አይጠወልግም ፤ ማለት ፡ በመስቀል ፡ የሚገኘው ፡ ክብር ፡ አይጠፋም ፤ ፍሬው ፡ ንብ ብር ፡ ነው ፤ ማለት ፡ በመስቀል ፡ የሚገኘው ፡ ክብር ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ ለፊት ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፡ ማለት ፡ መስቀል ፡ ለዓይን ፡ ሕሊና ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፤ ያንጊዜ ፡ ከሊቃን ፡ መላእክት ፡ አንዱ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ የዚህን ፡ ዕፅን ፡ ነገር ፡ ልታውቅ ፡ ትወዳለህ ? ማለት ፡ የጌታን ፡ መከራ ፡ ልታውቅ ፡ ትወዳለህ ? አለኝ ፤ ማወቅስ ፡ ሁሉንም ፡ ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፤ ይልቁንም ፡ የዚህን ፡ ዕፅ ፡ ነገር ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፤ ማለት ፡ ማወቅስ ፡ የጻድቃን ፡ የሰማዕታ ትን ፡ መከራ ፡ ላውቅ ፡ እወዳለሁ፤ ይልቁንም ፡ የጌታን ፡ መስቀል ፡ ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፤ ራሱ ፡ የጌታን ፡ ዙፋን ፡ የሚመስለው ፡

ረጅም ፡ ሁኖ ፡ ያየኸው ፡ በበጎ ፡ ነገር ፡ ሊጐበኛት ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ የሚቀመጥበት ፡ የእግዚአብሔር ዙፋን ፡ ነው ፡ ማለት ፡ ይህን ፡ ዓለም ፡ ለማዳን ፡ ሥጋውን ፡ ቁርሶ ፡ ደሙን ፡ አፍስሶ ፡ ባዳ ነው ፡ ጊዜ ፡ የሚሰቀልበት ፡ መስቀል ፡ ነው ፡ ከሥጋዊ ፡ ከደ ማዊ ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ ይነካው ፡ ዘንድ ፡ ሥልጣን ፡ የለውም ፡ ማለት ፡ ጸጋ ፡ ክብር የሚያሰጥ ፡ መስቀልን ፡ ማጥፋት ፡ የሚቻለው ፡ የለም ፡ አይሁድ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ሮማውያን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ የቀበሩት ፡ መስቀል ፡ ተነሥቶባቸዋልና ፡ ለተመረጡ ፡ ሰዎች ፡ ከዚህ ፡ ዕንጨት ፡ ፍሬ ፡ ይሰጣል ፡ ማለት ፡ በምግባር ፡ በሃ ይማኖት ፡ ለተመረጡ ፡ ሰዎች ፡ በመስቀል ፡ ከሚገኘው ፡ ክብር ፡ ይሰጣል ፡ ማለት ፡ ነው ፡ በመ ስዕ ፡ በኩል ፡ ይተከላል ፡ ማለት ፡ ወደመስዕ ፡ ፊቱን ፡ መልሰው ፡ ጌታን ፡ ሰቅለውታልና ፡ በመካን ፡ ቅዱስ ፡ ማለት ፡ በቀራንዮ ፡ መንገለ ፡ ቤቱ ፡ ማለት ፡ ቀራ ንዮ ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ አጠ ገብ ፡ ነውና ፡ ከዚህ ፡ ዕፅ ፡ በበሉ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፡ ማለት ፡ ይህን ፡ የመስቀልን ፡ ፀጋ ፡ ክብር ፡ ባገኙ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽመው ፡ ደስ ይላቸዋል ፡

ዕፀው ፡ ሁሉ ፡ በየወገናቸው ፡ መዓዛ ፡ ያገቡለታል ፡ ማለት ፡ ምዕመናን ፡ ለመስቀል ፡ ምስጋና ፡ ያገቡለታል ፡ መስቀል ፡ ኃይልነ ፡ መስቀል ፡ ጽንዕነ ፡ የማይለው ፡ የለምና ፡ ከዚህ ፡ ዕፅ ፡ የበሉ ፡ ሰዎች ፡ በሕይወት እንዲኖሩ ፡ እንግዲህም ፡ የሚነሱ ፡ ሰዎች ከዚህ ፡ ዕፅ ፡ እየበሉ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ፡ ማለት ፡ በመስቀል ፡ ተሰቅሎ ፡ ያድነናል ብለው ፡ አምነው ፡ በሕይወት ፡ እንደኖሩ ፡ ዛሬም ፡ በመስቀል ፡ ተሰቅሎ ፡ አድኖናል ፡ ብለው ፡ አምነው ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ፡ በዘመናቸው ፡ ይህን ፡ በበሉበት ወራት ፡ ኀዘን ፡ ድካም ፡ የለም ፡ ማለት ፡ መስቀልን ፡ ባመኑበት፡ ወራት ፡ ኀዘን ፡ ሥጋ ፡ ኃዘነ ፡ ነፍስ ፡ ድካመ ፡ ሥጋ ፡ ድካመ፡ ነፍስ ፡ የለባቸውም ፡ ይህን ፡ ዕፅ ፡ አዘጋጅቶላቸዋልና ፡ ይህን ዕፅ ፡ ይሰጧቸው ፡ ዘንድ ፡ አዝዟልና ፡ ማለት ፡ መስቀልን ፡ አዘጋጅቶላቸዋልና ፡ በመስቀል፡ የሚገኘውን ፡ ጸጋ ፡ ክብር ፡ ጻድቃን ፡ ለሆኑ ፡ ሰዎች ፡ አዘጋጅቷልና ፡ አመሰገንሁት ፡ አንድም ፡ ስድስቱ ተራሮች ፡ ማለት ፡ በስድስቱ ፡ ቃላተ ፡ ወንጌል ፡ ያመኑ ፡ ናቸው ፡ ሳብዕ፡ ደብር ፡ እመቤታችን ፡ ዕፀው ፡

ሁሉ ፡ ከበውታል ፤ ማለት ፡ የጻድቃን ፡ ንጽሕና ፤ ቅድስና ፡ ድንግልና ፡ ከበውታል ፡ ሲል ፡ ነው ፤ በውስጣቸው ፡ ያለውን፡ አንዱን ፡ የሚመስለው ፡ የለም፤ ማለት፡የእመቤታችንን፡ንጽሕና፡ ድንግልና ፤ ከጻድቃን ፡ ንጽሕና፡ ድንግልና፡የሚመስለው፡የለም ፤ ቅጠሉ ፡አበባው፡ አይጠወልግም ፡ ማለት፡በእመቤታችን፡ ድንግልና፡ የሚገኘው ፡ ክብር ፡ አይጠፋም ፤ ፍሬው ፡ እንደ ፤ ዘምባባ፡ ንብብር ነው ፤ ማለት ፡ በእመቤታችን ፤ ድንግልና ፡ የሚገኘው ፡ ክብር ፤ ብዙ ፤ ነው ፤ ለዓይን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነው ፤ ማለት ፡ በእ መቤታችን ፡ ድንግልና ፤ የሚገ ኘው ፡ ክብር ፡ ለዓይነ ፤ ልቡና ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነው ፤ ያንጊዜ ከሊቃነ ፤ መላእክት ፡ አንዱ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ የዚህን ፡ የዕፅ፡ ነገር ፡ ልታውቅ ፡ ትወዳለህ ? አለኝ፡ ማለት ፡ የእመቤታችንን ፤ ንጽሕናዋን ፡ ድንግልናዋን ፡ ልታውቅ ፡ ትወዳለህ ? አለኝ ፤ ማወቅስ ፡ መላውን ፡ ዕፅ ፡ ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፡ ይልቁንም ፡ የዚህን ፡ ዕፅ ፤ ነገር ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፤ ማለት ፡ ማወቅስ ፡ የጻድቃንንም ፡ ንጽሕና ፤ ድንግልና ፡ ላውቅ ፤ እወዳለሁ ፤ ይልቁንም ፡ የእመቤታችንን ፡ ድንግልና ፤ ንጽሕና ፤ ላውቅ ፡ እወዳለሁ ፡፡ አልሁት ፤ ራሱ ፤ የእግዚአብሔርን ፡ ዙፋን ፤ የሚመስል ፡ ረጅም ፡ ሁኖ ፡ የም ታየው ፡ ዓለምን ፡ በበጎ ፤ ነገር ፡ ይጐበኘው ፤ ዘንድ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፤ የሚቀመጥበት ፡ ዙፋኑ ፡ ነው ፤ ማለት ፡ ሰው ፡ ሁኖ ፡ ሥጋ ፡ ለብሶ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፤ የሚያ ድርባት ፤ እመቤታችን ፡ ናት ፤ ከሥጋዊ ፤ ከደማዊ ፡ አንዱም ፤ አንዱም ፡ ይህን ፡ ዕፅ ፡ ይነካው ፡ ዘንድ ፡ ሥልጣን ፡ የለውም ፤ ማለት ፡ የእመቤታችንን ፡ ንጽ ሕና ፤ ድንግልና ፡ የሚያጠፋው የለም ፤ አይሁድ ፡ እሩቅ ፡ ብእሲ ፡ ወልደ ፡ ዮሴፍ ፡ ብለውታል ፤ አንጢዲቁማርያጦስ ፡ ያፑስያው ያን ፤ ሲያውያን ፡ ዘውእቶሙ ፡ ፀረ ፡ ማርያም ፡ ይላቸዋል ፤ ባንድ ፡ ስም ፡ ሲሆን ፤ አንጢዲ ቁማርያጦስ ፡ ዘውእቱ ፡ ፀረ ፡ ማርያም ፡ እምድኅረ ወለደቶ ፡ ለእግዚእነ ፤ ተደመረት ምስለ ፡ ዮሴፍ ፤ ብሏል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ማጥፋት ፡ አልተቻላቸውም ፡ ይለዋል ፤ የዚህ ፡ ዕፅ ፡ ፍሬ፡ ለተመረጡ ፡ ሰዎች ፡ ይሰጣል፡ ማለት ፡ በእመቤታችን ፡ ድንግ ልና ፤ የሚገኘው ፡ ክብር ፡ በም ግባር ፡ በሃይማኖት ፡ ለተመረጡ ፡ ሰዎች ፡ ይሰጣል ፡ ማለት ፡ ነው ፤

መስዕ ፤ መካን ፤ ቅዱስ ፤ መንገስ ፡ ቤቱ ፡ ያለው ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ነው ፤ በእመቤታችን ፤ ጌታ ፡ ያድራል ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ይህን ፡ በበሉ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽመው ፡ ደስ ፡ ይላቸዋል ፤ ማለት ፡ በእመቤታችን ፡ ድንግልና ፡ የሚገኘውን ፡ ክብር ፡ ባገኙ ፡ ጊዜ ፡ ፈጽመው ፡ ሳይጠራጠሩ ፡ ደስ ይላቸዋል ፤ ዕፀው ፡ ሁሉ ፡ በየወገናቸው ፡ መዓዛቸውን ፡ ይሰጣሉ ፤ ማለት ፡ ምዕመናን ፡ ሁሉ ፡ ለእመቤታችን ፡ ምስጋና ያቀርባሉ ፤ ሰእሊ ፡ ለነ ፡ ቅድስት ፤ ሳትባል ፡ አትውልም ፡ አታድር ምና ፡ ነው ፤ ከዚህ ፡ ዕፅ ፡ የበሉ ፡ ሰዎች ፡ በሕይወት ፡ እንደኖሩ ፡ ዛሬም ፡ የሚነሡ ፡ ሰዎች ፡ ቢበሉ ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ፤ ማለት ፡ ከእመቤታችን ፡ ተወልዶ ፡ ያድነናል ፡ ብለው ፡ አምነው ፡ ያሉ ፡ በሕይወት ፡ እንደኖሩ ፤ ኋላም ፡ ከእመቤታችን ፡ ተወልዶ ፡ አድኖናል ፡ ብለው ፡ አምነው ፡ በሕይወት ፡ ይኖራሉ ፤ ይህን ፡ ዕፅ ፡ የበላ ፡ ሰው ፡ ኀዘን ፡ የለበትም ፤ ማለት ፡ በእመቤታችን ፡ ባመኑባት ፡ ወራት ፡ ኀዘነ ፡ ሥጋ ፤ ኀዘነ ፡ ነፍስ ፤ ድካመ ፡ ሥጋ ፤ ድካመ ፡ ነፍስ ፡ የለባቸውም ፤ የእመቤታችንን ፡ ድንግልና ፡ አዘጋጅቷልና ፤ በድንግልና ፡ የሚገኘውን ፡ ክብር ፡ ጻድቃን ፡

ስሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ይሰጧቸው ፡ ዘንድ ፡ ሰጧቸው ፡ ብሎ ፡ አሢልና ፡ አመሰገንኩት ፤ መጀመሪያ ፡ ወየ ዐውድዎ ፡ ብለህ ፡ ንባቡን ፡ ተርጉም ፤ ኋላ ፡ ሦስት ጊዜ ፡ እያወረድህ ፡ መልስ ፤

፳፫ ፤ ወእምህየ ፡ ሖርኩ ፡ ማዕከለ፡ ምድር ፡ ወርኢኩ ፡ መካነ ፡ ቡሩከ፤

ሰባቱን ፡ ተራራ ካየሁ ፡ በኋላ ፤ በሴም ፡ ዕጣ ፡ ሁሉ ፡ ሄድሁ ፤ ወጥሉለ ፤

እንተ ፡ ታውኀዝ ፡ ሀሊበ ፡ ወመዓረ ፡ የተባለች ፤

ዘቦቱ ፡ አዕፁቅ፡ ዘይነብር ፡ ወይሠርፅ እምዕፅ ፡ ዘተመትረ ፤

ተቈርጦ ፡ የተተከለ ፤ የለመለመ ፤ እንጨት ፡ ያለበት ፤ አንድም ፡ ከነቢያት ፡ በትንቢት ፡ የተወለዱ ፤ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ የከበሩ ፤ ሐዋርያት ፡ ያሉባት ፡ ኢየሩሳሌምን ፡ አየሁ ፤

[illegible] ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ደብረ ፡ ቅዱስ ፤

በዚያ ፡ ቦታ ፡ ቤተ ፡ መቅደስን ፡ አየሁ ፤

ወመትሕተ ፡ ደብር ፡ ማይ ፡ ዘመንገለ ፡ ጽባሑ ፤

ከተራራው ፡ በታች ፡ ከወደ ፡ ምሥራቁ ፡ ውኃ ፡ ይፈስሳል ፡ አለ ፤ ከነቢያት ፡ የሚገኝ ፡ ትምህርት በቤተ ፡ መቅደስ ፡ ይነገራል ፤

ወውኀዘቱ ፡ መንገለ ፡ ሰሜን ፤

አፈሳሰሱ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ነው ፤ የሚነገረው ፡ ለእስራኤል ፡ ነው ፤

፳፫ ፡ ወርኢኩ ፡ መንገለ ፡ ጽባሕ ፡ ካልአ ፡ ደብረ ፡ ዘይነውኅ ፡ እምዝ ፡

በምሥራቅም ፡ በኩል ፡ ከዚህ የረዘመ ፡ ተራራ ፡ ደብረ ፡ ታቦርን ፡ አየሁ ፡

፳፬ ፡ ወማዕከሎሙ ፡ ቈላ ፡ ዕሙቅ ፡

ብሔረ ፡ አሕዛብን ፡ አየሁ ፡

ወአልቦ ፡ ራሕብ ፡

ወርድ ፡ ስፋት ፡ የለውም ፡ አንድም ፡ ስፍሐ ፡ አዕምሮ ፡ የለውም ፡ ስፉሐ ፡ አእምሮም ይሳል ፡ ሳያናብብ ፡

ወሳቴኒ ፡ የሐውር ፡ ማይ ፡ መንገለ ደብር ፡

እመንገለ ፡ ደብር ፡ እንደማለት ከተራራው ፡ ውኃ ፡ ይፈስሳታል ፡ ከነቢያት ፡ የሚገኝ ፡ ትምህርት ለብሔረ ፡ አሕዛብ ፡ ይነገራል ፡

፳፭ ፡ ወመንገለ ፡ ዓረቡ ፡ ለዝ ፡ ካልእ ፡ ደብር ፡

በዚህ ፡ ተራራ ፡ በግራው ፡ በኩል ፡ ካልእ ፡ አርሞንኤም ፡ አለ ፡

ወይቴሐቶ ፡ ሎቱ ፡ ወአልቦ ፡ ኑኅ ወቈላ ፡ ታሕተ ፡ ማዕከሎሙ ፡

በዚህ ፡ በሁለተኛው ፡ ተራራ ፡ ምዕራብ ፡ አጠገብ ፡ ከእርሱ ፡ የሚያንስ ፡ ተራራ ፡ አርሞንኤም አለ ፡ (ያንሰዋል) ፡

፳፮ ፡ ወካልአት ፡ ቈላት ፡ ዕሙቃት ፡

ጥልቅ ፡ የሆኑ ፡ ቈላዎች ፡ አሉ ፡ አንድም ፡ በመካከላቸው ፡ በክህደት ፡ በኃጢአት ፡ ፍጹማን ፡ የሆኑ ፡ አሕዛብ ፡ የሚኖሩባቸው ብሔረ ፡ አሕዛብ ፡ አሉ ፡

ወይቡሳት ፡

ይቡሳን ፡ አእምሮ ፡ አሕዛብ ፡ የሚኖሩባት ፡

መንገለ ፡ ጽንፈ ፡ ፫ቲሆሙ ፡

በሦስቱ ፡ ተራራ ፡ አጠገብ ፡ በሐውርተ ፡ አሕዛብ ፡ አሉ ፡ ሳብዕ ፡ ደብር ፡ ያለውን ፡ የተረጐሙ ፡ እንደሆን ፡ ሌላ ፡ አመጣ ፡ ብሎ ፡ እንዲህ ፡ እንደ ተረጐምነው ፡ ብሎ ፡ መሄድ ፡ ሳብዕን ፡ ሳይተረጐሙ ፡ የመጡ ፡ እንደሆን ፡ ሦስቱን ፡ ተናገራቸው ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ደብረ ፡ ታቦር ፡ አርሞንኤም ፡ አራቱን ፡ በቃል ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ቀራንዮ ፡ እስክንድርያ ፡ ደብረ ፡ ቍስቋም ፡ አንድም ፡ ማዕከለ ፡ ምድር ፡ ወደ ኢየሩሳሌም ፡ ሄድሁ ፡ መካነ ፡ ቡሩክ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ደብር ፡ ቅዱስ ፡ ደብረ ፡ ዘይት ፡ ካልእ ፡ ደብረ ፡ ደብረ ፡ ታቦር ለዝ ፡ ደብር ፡ ካልእ ፡ አርሞንኤም ፡ ነው ፡ የቀረው ፡ ትርጓሜ ፡ አይለወጥም ፡ ወመንገለ ፡ ፫ቲሆሙ ፡ ፬ቲሆሙ ፡ እንደማለት ፡ በቤተ ፡ መቅደስ ፡ በደብረ፡ዘይት ፡ በደብረ ፡ ታቦር ፡ በአርሞንኤም ፡ አጠገብ ፡ በሐውርተ ፡ አሕዛብ ፡ አሉ ፡ ፯ቱን ፡ ለመምላት ፫ቱን በቃል ያመጧል ፡ ደብረ ፡ ሲና ፡

ቀራንዮ ፡ ከእስክንድርያና ፡ ከደብረ ፡ ቍስቋም ፡ አንዱን ፡ አግብቶ ፡ ነው ።

፹፱ ፤ ወኵሉ ፡ ቈላት ፡ ዕሙቃት ፤ ጥልቅ ፡ የሆኑ ፤

ወአልቦን ፡ ራሕብ ።

ስፋት ፡ የሌላቸው ፡ ቈላዎች ፡ አሉ ፤ አንድም ፡ በክህደት ፡ በኃጢአት ፡ ፍጹማን ፡ የሆኑ ፤ ስፍሐ ፡ አእምሮ ፡ የሌላቸው ፡ አሕዛብ ፡ የሚኖሩባቸው ፡ ብሔውርተ ፡ አሕዛብ ፡ አሉ ፤

እምኵኵሕ ፡ ጽኑዕ ፤

ከጽኑ ፡ ድንጋይ ፡ የተፈጠረ ፡ ጽኑ ፡ ድንጋይ ፡ አለ ፤ አንድም ስነ ፡ ፍጥረት ፤ አንድም ፡ ከጽኑዓን ፡ ልቡና ፡ አሕዛብ ፡ የተወለዱ ፡ አሕዛብ ፡ አሉ ፤

፺ ፤ ወዕፀ ፡ ይተከል ፡ በላዕሌሆን ፤

በእነርሱ ፡ ላይ ፡ ዕፀ ፡ ይተከላል ፡ አለ ፤ ሕግ ፡ ይሠራባቸዋል ፤

ወአንከርኩ ፡ በእንተ ፡ ኰኵሕ ፤

ስለ ፡ ፀሉቱ ፡ አደነቅሁ ።

ወአንከርኩ ፡ በእንተ ፡ ቈላት ፤

ስለ ፡ ሸለቆዎችም ፡ አደነቅሁ ፤ አለ ፤ የአሕዛብን ፡ ነገር ፡ አደነቅሁ ፤ ስለ ፡ እስራኤልም ፡ አደነቅሁ ።

ወጥቀ ፡ አንከርኩ ፤

ይልቁን ፡ የአሕዛብን ፡ ነገር ፡ አደነቅሁ ፡ አለ ፤ በብሔረ ፡ አሕዛብ ፡ አንፃር ፡ መካነ ፡ ኃጥአንን ፤ በብሔረ ፡ እስራኤል ፡ አንፃር ፡ መካነ ፡ ጻድቃንን ያሳየዋልና ፤

፺፩ ፤ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ እቤ ፡ በእንተ ምንት ፡ ዛቲ ፡ ምድር ፡ ቡርክት ፡ ወኵለንታሃ ፡ ዕፀወ ፡ ምልእት ።

ዕፀውን ፡ ሁለመናዋ ፡ የተመላች ፡ ይህች ፡ ቡርክት ፡ ምድር ፡ ለምን ፡ ተፈጠረች ? መንግሥተ ፡ ሰማያትን ።

፺፪ ፤ ወዛ ፡ ቈላ ፡ ርግምት ፡ ማዕከሎሙ ፤

ይህች ፡ ርግምት ፡ ቦታስ ፡ በመካከላቸው ፡ ለምን ፡ ተፈጠረች ? ገሃነመ ፡ እሳትን ፤

፺፫ ፤ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ አውሥአኒ ፡ ዑርኤል ፡ አሐዱ ፡ እመላእክት ፡ ቅዱሳን ፡ ዘሀሉ ፡ ምስሌየ ፤

ያን ፡ ጊዜም ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ከክበሩ ፡ ከመላእክት ፡ አንዱ ፡ ዑራኤል ፡ መለሰልኝ ፤

ወይቤለኒ ፡ ዛ ፡ ቈላ ፡ ርግምት ፡ ለርጉማን ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፤

እንዲህም ፡ አለኝ ፡ ይህች ፡ ርግምት ፡ ቦታ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ሊኖሩባት ፡ ለርጉማን ፡ ኃጥአን ፡ ተፈጠረች ፤

፺፬ ፤ ወዝየ ፡ ይትጋብኡ ፡ ኵሎሙ እለ ፡ ይብሉ ፡ በአፉሆሙ ፡ ላዕለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃለ ፡ ዘኢይደሉ ፤

በቃላቸው ፡ በእግዚአብሔር ፡ ላይ ፡ የማይገባ ፡ ነገርን ፡ የሚናገሩ ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ቦታ ፡ ይሰበሰባሉ ፤

፺፭ ፤ ወበእንተ ፡ ስብሐተ ፡ ዚአሁ ፡ ይትናገሩ ፡ ዕፁባተ ፡ ዝየ ፡ ያስተጋብ

ዕምሙ ፡ ወዝየ ፡ ምኵናኖሙ ፡ በደኃሪ ፡ መዋዕል ።
በጌትነቱ ፡ ላይ ፡ የማይገባ ፡ ቃልን ፡ የሚናገሩ ፡ ሰዎችን ፡ መላእክት ይሰበስቧቸዋል (አብነት ፡ መላእክት ፣ ሥላሴ ፣ አጋንንት ፡ ይሰበስቧቸዋል) ፡ ይላል ፡ በኋላኛው ፡ ዘመንም ፡ ፍርዳቸው ፡ በዚያ ፡ ይሆናል ።
፴፯ ፡ ወይከውን ፡ ላዕሌሆሙ ፡ አርአያ ፡ ኵነኔ ፡ ዘበጽድቅ ፡ በቅድመ ፡ ጻድቃን ።
በእውነት ፡ የሚደረግ ፡ የመቻያ ፍርድ ፡ በጻድቃን ፡ ፊት ፡ ይደረግባቸዋል ።
፴፰ ፡ ወኵሉ ፡ መዋዕለ ፡ በዝየ ይባርክዎ ፡ መሐርያን ፡ ለእግዚአ ስብሐት ፡ ንጉሥ ፡ ዘለዓለም ።
ለሰው ፡ የሚያዝኑ ፣ የሚራሩ ፡ ጻድቃን ፡ ለዘላለም ፡ የሚነግሥ ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታን ፡ በዘመኑ ፡ ሁሉ ፡ በዚያ ፡ ያመሰግኑታል ።
፴፱ ፡ ወበመዋዕለ ፡ ኵነኔሆሙ ፡ ይባርክዎ ፡ በምሕረቱ ፡ በከመ ፡ ከፈሎሙ ።
ይባርክዎ ፡ በምሕረቱ ፡ በከመ ፡ ከፈሎሙ ፡ በምሕረቱ ፡ ብሎ ፡ መግጠም ፡ ነው ፡ በተፈረደላቸው ፡ ወራት ፡ በቸርነቱ ፡ እንዳደላቸው ፡ በቸርነቱ ፡ ያመሰግኑታል ፡
፵ ፡ ውእተ ፡ ጊዜ ፡ አነኒ ፡ ባረክዎ ፡ ለእግዚአ ፡ ስብሐት ።
እኔም ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታን ፡ አመሰገንሁት ፡ ወሰቱ ፡ ነገርኩ ፡ ወዘከርኩ ፡ በከመ ይደሉ ፡ ለዕበዩ ።
ለገናንነቱም ፡ እንደሚገባ ፡ አድርጌ ፡ ጌትነቱን ፡ ተናገርሁለት ፡ ስሙንም ፡ ጠራሁ ።

## ምዕራፍ ፳
## ጉባኤ

፩ ፡ ወሖርኩ ፡ መንገለ ፡ ጽባሕ ፡ ማዕከላ ፡ ለደብረ ፡ መድበራ ።
በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ባለ ፡ ጽኑ በረሀ ፡ ባለበት ፡ ተራራ ፡ መካከል ፡ ሄድሁ ።
፪ ፡ ወርኢክዎ ፡ ገዳመ ፡ ባሕቲቶ ።
ጽኑ ፡ በረሀ ፡ ሁኖ ፡ አየሁት ፣ እንደ ፡ አብረንታት ፡ በሰሜን ፡ ያለ ሀገር ፡ ነው ።
፫ ፡ ወባሕቱ ፡ ምሉዕ ፡ ዕፀወ ፡ እምነ ፡ ዝንቱ ፡ ዘርዕ ።
ነገር ፡ ግን ፡ ከዘር ፡ የሚገኝ ፡ ዕፀውን ፡ (እንጨቶችን ፡) የተመላ ፡ ነው ፡ ጥንቱን ፡ ዘር ፡ የሌለው ፡ የለምና ፡ አንድም ፡ ከጻድቃን ፡ የተወለዱ ፡ ጻድቃን ፡ ያሉበትን መካነ ፡ ጻድቃንን ፡ አየሁ ።
፬ ፡ ወማይ ፡ እምላዕሉ ፡ ይፈለፍል ፡ በላዕሉ ።
ከላይ ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ውሀ ፡ ይመነጫል ።
እምላዕሉ ፡ በላዕሉ ፡ አለ ፡ የሚነገረው ፡ ትምህርቱ ፡ ሰማያዊ ፡ ነው ፡ የሚነገረው ፡ ርስት ፡ ሰማ

ያዊ ፡ ነውና ፤ የሚነገርላቸው ፡ ሰማያውያን ፤ ናቸውና ፤ ትምህርቱ ፡ ከላይ ፤ ይነገራል ፤
ያስተርኢ ፡ አስራብ ፡ ከመ ፡ ብዙኅ ፤ ዘይሰርብ ፤
ብዙኃ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ ፈሳሽ ፡ ብዙ ፡ ሁኖ ፡ ይፈስሳል ፡ ትምህርቱ ፡ ብዙ ፤ ሆኖ ፤ ይሰማል ፤
[redacted] ፤ ከመ ፡ መንገለ ፡ መስዕ ፡ መንገለ ፡ ዓረብ ፤
በመስዕ ፤ በኩል ፡ እንዲፈስስ ፤ ወደ ፤ ምዕራብም ፤ ይፈስሳል ፤ እንድም ፡ ትምህርቱ ፡ እንደ ፡ መስዕ ፡ በምዕራብ ፤ ይነገራል ፤
ወእምኮለሄኒ ፡ የዐርግ ፤
መስዕና ፡ ምዕራብን ፤ ሁለቱን ፤ ተናግሮ ፡ ነበርና ፤ በአራት ፤ መዓዝን ፡ ይነገራል ፤
ወእምህየኒ ፡ ማይ ፡ ወጠል ፤
ማይ ፡ ጠል ፡ በቁሙ ፤ እንድም ፡ ማይ ፡ ትምህርት ፤ ጠል ፡ ረድኤት ፡ ይሰጣል ፤
[redacted] ፤ ወሖርኩ ፡ ውስተ ፡ መካን ፡ ካልእ ፤ እምኒ ፡ መድበራ ፡ መንገለ ፡ ጽባሔ ፡ ለውእቱ ፡ ደብር ፡ ቀረብኩ ፤
ለዚህ ፤ ተራራ ፡ ምሥራቁ ፤ ወደ ፡ ሆነ ፤ ወደ ፤ ምሥራቁ ፡ ቦታ ፡ ሄድሁ ፤
[redacted] ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ዕፀወ ፡ ኰነኔ ፤
ሴቶች ፤ ቀምመው ፡ ተቀብተዋቸው ፡ በወንዶች ፡ መቻያ ፡ የሚያመጡትን ፡ ዕፀው ፡ አየሁ ፤ እንድም ፡ ሥርዓት ፤ የተሠራባቸውን ፡ ዕፀው ፡ አየሁ ፤ እንድም ፡ ቢያፈርሷቸው ፡ የሚያስፈርዱትን ፡ ሕግጋት ፡ አየሁ ፤ እንድም ፡ ሕግ ፡ የሚጠብቁ ፡ ጻድቃንን ፡ አየሁ ፤
ፈድፋደ ፤ ቁላቁለ ፡ መዓዛ ፤
ብዙ ፡ የሽታ ፡ ቅመም ፡ ያለባቸው ፤ እንድም ፡ የሃይማኖት የምግባር ፡ ቅመም ፡ ያለባቸው ጻድቃንን ፡ አየሁ ፤
ዘስሂን ፡ ወከርቤ ፤
የነጭ ፡ ዕጣን ፡ የከርቤ ፡ መዓዛ የሚሆን ፤
ወዕፀውኒ ፡ ኢይትማሰሉ ፤
እንጨቶችም ፡ በመዓዛ ፡ በመልክ ፡ አይመሳሰሉም ፤ እንድም ፡ ጻድቃን ፡ በገድል ፡ በትሩፋት ፡ አይመሳሰሉም ፤
፰ ፤ ወላዕሌሁ ፡ ላዕለ ፡ እሉንቱ ፡ ላዕለ ፡ ደብረ ፡ ጽባሕ ፡ ወአኮ ፡ ርኁቅ ፤
እነሱንም ፡ ካየሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ምሥራቅ ፡ ተራራ ፡ ሄድሁ ፤ ፈጽሜም ፡ የራቅሁ ፡ አይደለሁም ፤
፱ ፤ ወርኢኩ ፤ መካነ ፡ ካልአ ፡ ቁላተ ማይ ፡ ከመ ፡ ዘኢይትዌዳዕ ፤
ከመ ፡ ቀረ ፤ ነው ፤ ላዕሌሁ ፡ ላዕለ ፡ እሉንቱ ፡ ላዕለ ፡ ደብር እንድ ፡ ወገን ፡ ነው ፤ ሩቅ ፡ ሆኜ ፡ ያይደለ ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡ የማይገታ ፡ ውኃ ፡ ያለበት ፡ ቈላ ፡ አየሁ ፤ እንድም ፡ የማይ ፈጸም ፤ ትምህርት ፡ ያለበት ፡ መካነ ፡ ጻድቃንን ፡ አየሁ ፤

፲ ፡ ወርኢኩ ፡ ዕፀ ፡ ሠናየ ፡ ወመዓዛሁ ፡ ከመ ፡ ዘስኪኖን ፤
መዓዛው ፡ እንደ ፡ ለውዝ ፡ እንደ ፡ ገውዝ ፡ ያለ ፡ እንጨትን ፡ አየሁ ፤ አንድም ፡ ምግባሩ ፤ ሃይማኖቱ ፡ እንደ ፡ አብርሃም ፡ የሆነ ፡ ጻድቅን ፡ አየሁ ፤
፲፩ ፤ ወመንገለ ፡ ክነፊሆሙ ፡ ለቈላት ፡ እሉንቱ ፡ ርኢኩ ፡ ቀናንሞስ ፡ ዘመዓዛ ፤
ጽንፈሆሙ ፡ ሲል ፡ ነው ፤ በእነዚህ ፡ ቈላዎች ፡ አጠገብ ፡ ቀናንሞስ ፡ ደርስኔ ፡ አየሁ ፤ አንድም ፡ ምዑዘ ፡ ምግባር ፡ ወሃይማኖት ፡ የሆነ ፡ ጻድቅን ፡ አየሁ ፤
፲፪ ፤ ወዲበ ፡ እልክቱ ፡ ቀረብኩ ፡ ዘመንገለ ፡ ጽባሕ ፤
እኒህን ፡ ካየሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ቀረብሁ ፤
ወርኢኩ ፡ ካልአ ፡ ደብረ ፡ ዘቦ ፡ ውስቴቱ ፡ ዕፀው ፤
ዕፀው ፡ ያሉበትን ፡ ሌላ ፡ ቦታን ፡ አየሁ ፤ ስነ ፤ ፍጥረትን ፤ አንድም ፡ ጻድቃን ፡ ያሉበትን ፡ ቦታ ፡ አየሁ ፤ መካነ ፡ ጻድቃን ፡ ነው ፤
፲፫ ፤ ወይወጽእ ፡ ማይ ፡ እምኔሁ ፡ ከመ ፡ ነቀጥሮ ፡ ዘስሙ ፡ ሣሬራ ፡ ወከልበኔ ፤
ባንዱ ፡ ልሳን ፡ ሣሬራ ፡ የሚባል ፡ ጽሩይ ፡ ውኃ ፡ አየሁ ፤ በእርሱ ፤ ሲፈስስ ፡ አየሁ ፤ ነቀጥሮ ፡ ምዑዝ ፡ ነው ፤ ምዑዝ ፡ ውኃ ፡ ሲፈስስ ፡ አየሁ ፤ አንድም ፡ በእርሱ ፡ ያማረ ፡ የተወደደ ፡ ትምህርት ፡ ሲነገር ፡ ሰማሁ ፤ ወከልበኔ ፤ ልባንጃ ፡ ሽቱ ፡ ነው ፤ አንድም ፡ ምዑዝ ፡ ትምህርት ፡ በእርሱ ፡ ይነገራል ፤
፲፬ ፤ ወዲበ ፡ ውእቱ ፡ ደብር ፡ ርኢኩ ፡ ካልአ ፡ ደብረ ፤
በዚያም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ሆኜ ፡ ሌላ ፡ ተራራን ፡ አየሁ ፤
ወውስቴቱ ፡ ዕፀው ፡ ዘአልዋ ፤
በውስጡም ፡ ዋግራ ፡ የሚባሉ ፡ እንጨቶች ፡ አሉበት ፤ ዋግራ ፡ ሽቱ ፡ ነው ፤ አንድም ፡ ጽኑ ፡ ነው ፤ በምግባር ፡ በሃይማኖት ፡ የጸኑ ፡ ጻድቃን ፡ አሉበት ፤
፲፭ ፤ ወእልክቱ ፡ ዕፀው ፡ ምሉዓን ፡ ዘከመ ፡ ከርካዕ ፡ ዘጽኑዕ ፤
እነዚህ ፡ እንጨቶች ፡ እንደፅኑ ፡ እንጨት ፡ እንደ ፡ ሎሚ ፡ ያለ ፡ ሽቱ ፡ የተመሉ ፡ ናቸው ፤ አንድም ፡ እሊህ ፡ ጻድቃን ፡ እንደ ፡ አብርሃም ፡ በምግባር ፡ በሃይማኖት ፡ የጸኑ ፡ ናቸው ፤
ወሶበ ፡ ይነሥእዎ ፡ ለውእቱ ፡ ፍሬ ፡ ይኄይስ ፡ እምኵሉ ፡ አፈው ፤
የዚህን ፡ ፍሬ ፡ ባነሡት ፤ በያዙት ፡ ጊዜ ፡ ከሽቱ ፡ ሁሉ ፡ ይበልጣል ፤ አንዱ ፡ ጻድቅ ፡ ካንዱ ፡ ጻድቅ ፡ ይበልጣል ፤
፲፮ ፤ ወእምድኅረ ፡ እሉ ፡ አፈው ፡ ለመስዕ ፡ እንዘ ፡ እኔጽር ፡ መልዕልተ አድባር ፤

እሊህን ፡ ሽቱዎች ፡ ካየሁ ፡
በኋላ ፡ ወደመስዕ ፡ ስመለከት ፤
፲፯ ፤ ወርኢኩ ፡ ፯ተ ፡ አድባረ ፡
ምሉዓነ ፡ ስንበልት ፡ ቅድው ፤
ያማረ ፡ ልባንጃ ፡ ሽቱ ፡ የተመሉ ፡
ሰባት ፡ ተራራዎችን ፡ አየሁ ፤
ወዕፀወ ፡ መዓዛ ፡ ወቀናንሞስ ፤
ወጥጥሬ ፤
ደርስኒ ፡ ሽቱ ፤ ጥሩ ፡ ሽታ ፡
ያላቸው ፡ እንጨቶችንም ፡ አየሁ ፤
ጥጥሬ ፤ የሚባል ሽቱ ፡ የተመ
ላባቸው ፡ ሰባት ፡ ተራራዎችን ፤
አየሁ ፤ አንድም ፡ ምዑዛነ ፡
ምግባር ፡ ወሃይማኖት ፡ የሚሆኑ ፡
ጻድቃን ፡ የተመሉባት ፡ መካነ ፡
ጻድቃንን ፡ አየሁ ፤
፲፰ ፤ ወእምህየ ፡ ሖርኩ ፡ መልዕ
ልተ ፡ ርእሶሙ ፡ ለእልክቱ ፡ አድባር ፡
እንዘ ፡ ርኁቅ ፡ ውእቱ ፡ ለጽባሕ ፤
ሖርኩ ፡ ለጽባሕ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
በዚህ ፡ በተራሮች ፡ ራስ ፡ ላይ
ሩቅ ፡ ሁኜ ፡ ሳለሁ ፤ ወደምሥ
ራቅ ፡ ሄድሁ ፤ ርኁቅ ፡ የወርድ ፡
የቁመት ፡ ነው ፡
፲፱ ፤ ወኀለፍኩ ፡ እንተ ፡ ባሕረ ፡
ኤርትራ ፡ ወእምኔሁ ፡ ርኁቀ ፡ ክንኩ ፤
ወደ ፡ ኤርትራ ፡ ባሕርም ፡ ሄድሁ ፤
ከዚያም ፡ ቦታ ፡ የራቅሁ ፡ ሆንኩ ፤
፳ ፤ ወኀለፍኩ ፡ መልዕልቶ ፡ ለመ
ልአክ ፡ ዙጡኤል ፤
ቂጥኤልም ፡ ይላል ፤ ዓቃቤ ፡
ገነት ፡ ነው ፤ በሩን ፡ ሲጠብቅ ፡
ላዩን ፡ አልፎት ፡ ሄዷል ፤

ወመጻእኩ ፡ ውስተ ፡ ገነተ ፡ ጽድቅ ፤
በቸርነቱም ፡ ወደምትወረስ ፡
ገነት ፡ መጣሁ ፡
፳፩ ፤ ወርኢኩ ፡ ክሃ ፡ ከሃቲሆሙ ፡
ለእልኩ ፡ ዕፀው ፡ ዕፀወ ፡ ብዙኃነ ፤
ከዚህ ፡ ዕፀ ፡ ወዲያ ፤ ወዲያ ፡ ያለ
ውን ፡ ዕፀ ፡ አየሁ ፤ አንድም ፡
ከባቲሆሙ ፡ ቢል ፡ ከእሊህ ፡ ዕፀ ፤
ወዲያ ሆኜ ፡ ብዙ ፡ ዕፀውን ፡
አየሁ ፤
ወዓቢያነ ፡ ይበቍሉ ፡ በህየ ፤
ታላላቆች ፡ የሽቱ ፡ እንጨቶችን
በዚያ ፡ በቅለው ፡ አየሁ ፤ የሽቱ
እንጨት ፡ ጥቃቅን ፡ ነው ፤ እሊህ ፡
ግን ፡ ታላላቆች ፡ ናቸው ፤
[redacted] ፤ ወእንዘ ፡ ፄናሆሙ ፡ ሠናይ ፡
ዓቢያን ፤
ሽታቸውም ፡ ያማረ ፤ ሲሆን ፤
ታላላቆች ፤ ናቸው ፤
ወሰናሙ ፡ ብዙኅ ፤
ብርሃናቸውም ፡ ብዙ ፡ ነው ፤
ወስቡሓን ፤
ብሩሃን ፡ ናቸው ፤
፳፪ ፤ ወዕፀ ፤ ጥበብ ፤
ቢበሉት ፡ ክፉ ፡ ጥበብ ፤ ባይበ
ሉት ፡ በጎ ፡ ጥበብ ፤ የሚገለጥ
በት ፡ ዕፀን ፡ አየሁ ፤
ዘእምኔሁ ፡ በሊያሙ ፡ የአምርዋ ፤
ለጥበብ ፤ ዓባይ ፤
አዳምና ፡ ሔዋን ፡ ከእርሱ ፡ በል
ተው ፡ ታላቋን ፡ ጥበብ ፡ የሚያወ
ቁባት ፤
ወይመስል ፤ ሐመረ ፡ ጽራእ ፤
ተረርቃሞ ፤ ይመስላል ፤

፳፬ ፥ ወፍሬሁኒ ፡ ከመ ፡ አስካለ ፡ ወይን ፡ ጥቀ ፡ ሠናይ ፤
ፍሬውም ፡ የወይን ፡ ዘለላ ፡ ይመስላል ፤
ወጼናሁ ፡ ለውእቱ ፡ ዕፅ ፡ የሐውር ፡ ወይበጽሕ ፡ ነዋሀ ፤
የዚያም ፡ እንጨት ፡ ሽታው ፡ ሂዶ ፡ ከሩቅ ፡ ይደርሳል ፤
፳፭ ፥ ወእቤ ፡ ዝ ፡ ዕፅ ፡ ሠናይ ፡ ወከመ ፡ ሠናይ ፡ ወፍሡሕ ፡ ርእየቱ ፤
መልኩ ፡ ያማረ ፡ እንደመሆኑ ፣ ሊያውቁትም ፡ ደስ ፡ እንደማሰኘቱ ፡ ይህ ፡ እንጨት ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነው ፡ አልሁ ፤
፳፮ ፥ ወአውሥአኒ ፡ ቅዱስ ፡ ሩፋ [illegible] መልአክ ፡ ዘምስሌየ ፡ ሀሎ ፤
ከእኔ ፡ ጋር ፡ ያለ ፡ የከበረ ፡ መልአኩ ፡ ሩፋኤልም ፡ መለሰልኝ ፤
[redacted] ፥ ወይቤለኒ ፡ ዝውእቱ ፡ ዕፀ ፡ ጥበብ ፡ ዘእምኔሁ ፡ በልዑ ፡ አበውከ ፡ አረጋዊ ወእምከ ፡ ዐቢራይት ፡ እለ ፡ ቀደሙከ ፤
ሽማግሌ ፡ አባትህ ፡ አዳምና ፡ ባልቴት ፡ እናትህ ፡ ሔዋን ፡ ከአንተ ፡ አስቀድመው ፡ የነበሩ ፡ ከሱ ፡ በልተው ፡ ዓይናቸው ፡ የተፈታበት ፡ ጥበብን ፡ የሚገልፅ ፡ ዕፀ ፡ በለስ ፡ ይህ ፡ ነው ፤
የበጎ ፡ ተፈትሖ ፡ ብሎ ፡ ነበር ፡ የክፉ ፡ ሁናባቸዋል ፤
[redacted] ፥ ወአእመርዎ ፡ ለጥበብ ፡ ወተፈትሐ ፡ አዕይንቲሆሙ ፤
ከእርሱም ፡ በልተው ፡ ክፉ ፡ ጥበብን ፡ አወቋት ፣ ዓይኖቻቸውም ፡ ተገለጡ ፤
ወአእመሩ ፡ ከመ ፡ ዕራቃኒሆሙ ፡ ሀለዉ ፤
ራቍታቸውንም ፡ እንዳሉ ፡ ዐወቁ ፤
እንደ ፡ ምን ፡ መልካም ፡ ኑሮ ፡ እንኖር ፡ ኑሯል ፡ ብለዋልና ፤
ወተሰዱ ፡ እምገነት ፤
ከገነትም ፡ ተሰደዱ ፡ አለኝ ፤
፳፱ ፥ ወእምህየ ፡ ሖርኩ ፡ እስከ ፡ አጽናፈ ፡ ምድር ፤
ከዚያም ፡ እስከ ፡ ምድር ፡ ዳርቻ ፡ ድረስ ፡ ሄድኩ ፤
ወርኢኩ ፡ በህየ ፡ አራዊተ ፡ ዓበይተ ፤
በዚያም ፡ ግሩማን ፡ አራዊትን ፡ አየሁ ፤
፴ ፥ ወይትዌለጥ ፡ አሐዱ ፡ እምኩልኡ ፤
አንዱም ፡ ከአንዱ ፡ ልውጥ ፡ ነው ፤
ወአዕዋፍኒ ፡ ይትዌለጥ ፡ ገጾሙ ፡ ወስናሙ ፤
የወፎችም ፡ ፊታቸው ፡ ጠጕራቸውም ፡ ይለወጣል ፤
ወቃሎሙሂ ፡ ይትዌለጥ ፡ አሐዱ ፡ እምካልኡ ፤
ቋንቋቸውም ፡ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ይለወጣል ፤
፴፩ ፥ ወበጽባሒሆሙ ፡ ለእሉ ፡ አራዊት ፡ ርኢኩ ፡ አጽናፈ ፡ ምድር ፡ በኀበ ፡ ሰማይ ፡ የዐርፍ ፤

በእኒህ ፡ አውሬዎችም ፡ አጠ
ገብ ፡ በምድር ፡ ዳርቻ ፡ ሰማይ
በላዩ ፡ ያረፈበት ፡ አድማስን ፡
አየሁ ፤

ውኀዋኀወ ፡ ርኀዎተ ፤
የተከፈቱ ፡ ደጃፎችንም ፡ አየሁ ፤

፴፱ ፤ ወርኢኩ ፡ እፎ ፡ ይወፅኡ ፡
ከዋክብተ ፡ ሰማይ ፡ ወኍለቁ ፡ ዘእም
ኒሁ ፡ ይወፅኡ ፡ ኀዋኀወ ፤
ዘእምኒሁ ፡ ይወፅኡ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
ከሱ ፡ ከዋክብት ፡ የሚወጡበት ፡
ኀዋኀውን ፡ አየሁ ፤ ከዋክብት ፡
የሚወጡባቸው ፡ ደጃፎችንም ፡
ቆጠርሁ ፤

፵ ፤ ወጸሐፍኩ ፡ ኵሎ ፡ መውፅኦሙ
ለለአሐዱ ፡ አሐዱ ፡ በበኍልቆሙ ፤
የያንዳንዱን ፡ መውጫ ፡ ሁሉ ፡
በየቍጥራቸው ፡ ጻፍሁ ፤
ወአስማቲሆሙ ፡ በደርኆሙ ፤
ስማቸውን ፤
ወምንባሮሙ ፤
አኗኗራቸውን ፤
ወጊዜሆሙ ፤
ጊዜያቸውን ፡
ወአውራኂሆሙ ፤
ወራታቸውን ፤
በከመ ፡ አርአየኒ ፡ ኡርኤል ፡
መልአክ ፡ ዘምስሌየ ፡ ሀሉ ፤
ከእኔ ፡ ጋራ ፡ ያለ ፡ መልአኩ ፡
ዑራኤል ፡ እንዳሳየኝ ፡ በአንድ
ነት ፡ ጻፍሁ ፤

፵፩ ፤ ወኵሎ ፡ አርአየኒ ፡ ሊተ ፡
ወጸሐፎ ፤
ሁሉንም ፡ ለእኔ ፡ አሳየኝ ፡
ጻፈው ፤
ወዓዲ ፡ አስማቲሆሙ ፡ ጸሐፈ ፡ ሊተ ፤
ወጸሐፈ ፡ ሊተ ፡ ሲል ፡ ነው ፤
ስማቸውን ፡ ጻፈልኝ ፤ አንድም
ወጸሐፎ ፡ ቢል ፡ ስማቸውን ፡
ጻፈው አለኝ ፤
ወትእዛዛቲሆሙ ፤
ሥርዓታቸውን ፤
ወምግባራቲሆሙ ፤
ሥራቸውን ፡ (ምግብናቸውን) ፤

፵፪ ፤ ወእምህየ ፡ ሖርኩ ፡ መንገለ ፡
መስዕ በአጽናፈ ፡ ምድር ፤
ከዚያም ፡ ተነሥቼ ፡ በምድር ፡
ዳር ወደ ፡ መስዕ ፡ ሄድኩ ፤
ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ መንክረ ፡ ዓቢየ ፡
ወስቡሐ ፡ በአጽናፈሃ ፡ ለኵላ ፡ ምድር ፤
በዚያም ፡ ሳለሁ ፡ በምድር ፡ ሁሉ ፡
ዳርቻ ፡ የሚያበራ ፡ ታላቅ ፡ ተአ
ምራትን ፡ አየሁ ፤

፵፫ ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ኀዋኀወ ፡
ሰማይ ፡ ፍቱሐተ ፡ በሰማይ ፡
ሠለስተ ፤
በመስዕ ፡ በኵል ፡ የተከፈቱ ፡
ሦስት በሮችን ፡ አየሁ ፤
በበአሐዱ ፡ እምኒሆሙ ፡ ይወፅኡ ፡
ነፋሳት ፤
ከዚያም ፡ በየአንዳንዱ ፡ ነፋሳት
ይወጣሉ ፡

፵፬ ፤ ወመንገለ ፡ መስዕ ፡ ሶበ ፡
ይነፍሕ ፡ ቍር ፡ ወበረድ ፤

በመስዕ ፡ በኩል ፡ ነፋስ ፡ በነፈሰ
ጊዜ ፡ ቀቅ ፡ ክፉ ፡ ቊር ፤
ወበረድ ፤
የከፋ ፡ በረድ ፤
ወአስሐትያ ፤
ውርጭ ፤
ወሐመዳ ፡
ዋግ ፡
ወጠል ፤
ጤዛ ፤
ወዝናም ፤
የከፋ ፡ ዝናም ፡ ይሆናል ፤
ወእምአሐቲ ፡ ኆኅት ፡ በሠናይ ፡
ይነፍሕ ፤
በአንዲቱ ፡ መስኮት ፡ በበጎ ፡
ይነፍሳል ፤
[illegible] ፤ ወሶበ ፡ በክልኤሆሙ ፡
ኆኆኅው ይነፍሑ ፡ በኃይል ፤
በሁለቱ ፡ መስኮቶች ፡ ሁሉ ፡
በነፈሱ ፡ ጊዜ ፡ በኃይል ፡ በር
ትተው ፡ ይነፍሳሉ ፤
ወጻዕር ፡ ይከውን ፡ ዲበ ፡ ምድር ፤
በዚህም ፡ ዓለም ፡ ጽኑ ፡ መከራ
ይሆናል ፤
ወበኃይል ፡ ይነፍሑ ፤
እነሱም ፡ በኃይል ፡ ይነፍሳሉ ፤
[illegible] ፤ ወእምህየ ፡ ሖርኩ ፡ መንገለ ፡
ዓረብ ፡ በአጽናፈ ፡ ምድር ፤
ከዚያም ፡ ቦታ ፡ በምድር ፡ ዳርቻ ፡
ወደ ፡ ፀሐይ ፡ መግቢያ ፡ ሄድኩ ፡
ወርኢኩ ፡ በህየ ፡ ሠለስተ ፡ ኆዋኅወ ፡
ርኅዋተ ፡ በከመ ፡ ርኢኩ ፡ በምሥ
ራቅ ፡ በአምጣነ ፡ ኆዋኅው ፡ ወበአምጣነ ፡
ሙፃኡ ፤
በምሥራቅ ፡ በኩል ፡ ባሉት ፡
ኆዋኅው ፡ መጠን ፡ በመውጫው ፡
ልክ ፡ የተከፈቱ ፡ ሦስት ፡ መስኮ
ቶችን ፡ አየሁ ፡
፶ ፤ ወእምህየ ፡ ሖርኩ ፡ መንገለ ፡
ዓዜብ ፡ በአጽናፈ ፡ ምድር ፤
ከዚያም ፡ ቦታ ፡ በምድር ፡ ዳርቻ ፡
ወደ ፡ አዜብ ፡ ሄድኩ ፤
፶፩ ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ፫ተ ፡ ኆዋ
ኅወ ፡ ሰማይ ፡ ርኅዋተ ፤
በዚያም ፡ ቦታ ፡ የተከፈቱ ፡
ሦስት ፡ የሰማይ ፡ መስኮቶችን ፡
አየሁ ፤
ወይወፅእ ፡ እምህየ ፡ አዜብ ፤
በዚያም ፡ ቦታ ፡ ውዑይ ፡ ነፋስ ፡
ይነፍሳል ፤
ወጠል ፡ ወዝናም ፡ ወነፋስ ፤
ጤዛ ፤ ዝናም ፤ ነፋስ ፡ ይነፍሳል ፤
[illegible] ፤ ወእምህየ ፡ ሖርኩ ፡ መንገለ ፡
ጽባሕ ፡ በአጽናፈ ፡ ሰማይ ፤
ከዚያም ፡ ቦታ ፡ ተነሥቼ ፡ በሰማይ
ዳርቻ ፡ ወደ ፡ ፀሐይ ፡ መውጫ ፡
ሄድኩ ፡ ከዚህ ፡ እንደ ፡ እርእስት ፡
ተናገርሮታል ፡ ኋላ ፡ በደግ ፡ ያመ
ጣዋል ፤
ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ሠለስተ ፡ ኆዋኅወ ፡
ሰማይ ፡ ርኅዋተ ፡ መንገለ ፡ ጽባሕ ፤
በዚያም ፡ ቦታ ፡ ሳለሁ ፡ በፀሐይ ፡
መውጫ ፡ በኩል ፡ የተከፈቱ ፡
ሦስት ፡ የሰማይ ፡ ደጃፎችን ፡
አየሁ ፤

፺፫ ። ወበላዕሌሆሙ ፡ ኀዋኀው ፡ ንኡሳን ፡ በበአሐዱ ፡ እምእልኩ ፡ ኀዋኀው ፡ የኃልቆ ፡ ንኡሳን ፡ ከዋክብተ ፡ ሰማይ ።

በታናናሾቹ ፡ ደጃፎችም ፡ ላይ ፡ ከእነዚህ ፡ ደጃፎች ፡ በያንዳንዱ ታናናሾች ፡ የሰማይ ፡ ኮከቦች ፡ ይገቡበታል ። መስኮቶችስ ፡ ዓቢያን ፡ ናቸው ። ንኡሳን ፡ ከዋክብት ፡ ስለወጡባቸው ፡ ስለገቡባቸው ፡ ንኡሳን ፡ አሏቸው ።

፺፬ ። ወየሐውሩ ፡ ምዕራበ ፡ በፍኖት ፡ እንተ ፡ ተርእየት ፡ ሎሙ ።
ተሠርዐት ፡ ሎሙ ፡ ሲል ፡ ነው ። በተሠራችላቸው ። አንድም ፡ እንደ ፡ ንባቡ ፡ ተርጕም ። እኒ ፡ ባየሁላቸው ፡ ጐዳና ፡ ወደፀሐይ ፡ መግቢያ ፡ ይሔዳሉ ።

፺፭ ። ወሶበ ፡ ርኢኩ ፡ ባረኩ ።
ይህንም ፡ በአየሁ ፡ ጊዜ ፡ አመሰገንሁ ።
ወበኵሉ ፡ ጊዜ ፡ እባርኮ ፡ ለእግዚአ ፡ ስብሐት ።
በየጊዜውም ፡ የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታን ፡ አመሰግነዋለሁ ።
ዘገብረ ፡ ተአምራተ ፡ ዓቢያነ ፡ ወስቡሓነ ፡ ከመ ፡ ያርኢ ፡ ዕበየ ፡ ግብሩ ፡ ለመላእክቲሁ ፡ ወለነፍሳተ ፡ ሰብእ ።
የፍጥረቱን ፡ ገናንነት ፡ ለሰዎችና ፡ ለመላእክት ፡ ሲገልጥ ። የክብር ፡ ባለቤት ፡ ጌታንም ፡ በየጊዜው ፡ አመሰግነዋለሁ ፡

፺፮ ። ከመ ፡ ይሰብሑ ፡ ግብሮ ።
ሥራውን ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ።
ወኵሉ ፡ ተግባሩ ፡ ከመ ፡ ይርአዩ ፡ ግብረ ፡ ኃይሉ ።
ፍጥረቱም ፡ ሁሉ ፡ የኃይሉን ፡ ሥራ ፡ ያዩ ዘንድ ።
ወይሰብሕዎ ፡ ለግብረ ፡ እደዊሁ ፡ ዓቢይ ።
ታላቅ ፡ የሆነ ፡ የከሃሊነቱንም ፡ ሥራ ፡ ያመሰግኑ ፡ ዘንድ ።
ወይባርክዎ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።
ስነ ፡ ፍጥረቱም ፡ እሱን ፡ ለዘለዓለሙ ፡ ያመሰግኑት ፡ ዘንድ ፡ ይህንን ፡ አደረገ ።

## ምዕራፍ ፱
## ጉባኤ

[illegible] ። ራእይ ፡ ዘርእየ ፡ ካልአ ፡ ራእየ ፡ ጥበብ ፡ ዘርእየ ፡ ሄኖክ ፡ ወልደ ፡ ያሬድ ።
ራእይና ፡ ራእይ ። ዘርእየና ፡ ዘርእየ ፡ ሄኖክ ፡ አንድ ፡ ወገን ። ሄኖክ ፡ ያየው ራእይ ፡ ይህ ፡ ነው ። አንድም ፡ ካልአ ፡ ራእየ ፡ የያሬድ ፡ ልጅ ፡ ሄኖክ ፡ በሌላ ፡ ጊዜ ፡ ያየው ፡ ራዕይ ፡ ይህ ፡ ነው ።
ወልደ ፡ መላልኤል ።
ያሬድን ፡ የመላልኤል ፡ ልጅ ፡ አለው ።
ወልደ ፡ ቃይናን ።
መላልኤልን ፡ የቃይናንን ፡ ልጅ ፡ አለው ።
ወልደ ፡ ሄኖስ ።

ቃይናንን ፡ የሄኖስ ፡ ልጅ ፡
አለው ።
ወለደ፡ ሴት ።
ሄኖስን ፡የሴት ፡ ልጅ ፡ አለው ፡
ወለደ ፡ አዳም ።
ሴትን ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ አለው
ሽቅብ ፡ ይቆጥራል ።
፱ ፡ ወዝ ፡ ርእሱ ፡ ለነገረ ፡ ጥበብ ።
ግብረ ፡ ጥበብ ፡ ሲል ፡ነው ።
ዘአንሣእኩ ፡ እትናገር ።
በዚህም ፡ ዓለም ፡ ላሉ ፡ ሰዎች
እናገር ፡ ዘንድ ፡ የጀመርኩት ፡
የዘጠኙ ፡ ሕገጋት ፡ አበጋዝ ፡
ኢታምልክ ፡ ይህ ፡ የጥበብ ፡
ነገር ፡ መጀመሪያና መጨረሻ ፡
ነው ።
ወእብል ፡ ለእለ ፡ የኀድሩ ፡ ዲበ ፡
የብስ ።
በዚህ ፡ ዓለም ፡ ላሉ፡ ሰዎች፡እና
ገር ፡ ዘንድ ፡ አበው ፡ ስሙ ።
፲ ፡ ስምዑ ፡ ቀደምት፡ ወርእዩ ፡
ደኃርያን ፡ ነገረ ፡ ቅዱስ።
በኋላም ፡ የተነሣችሁ ፡ ውሉድ
የምናገረውን ፡ ስሙ ። ይህን ፡
ልዩ ፡ ነገር ፡ ስሙ ።
እለ ፡ እነግር ፡ ቅድመ ፡ እግዚአ ፡
መናፍስት ።
እግዚአ ፡ መላእክት ፡ እግዚአ
ሀብታት ፡ እግዚአ ፡ ነፋሳት ።
እግዚአ፡ ነፍሳት፡ ሲል ፡ ነው ።
መላእክት ፡ ከጌታ ፡ ፊት ፡ የም
ናገረውን ፡ የከበረ ፡ የኢታም
ልክን ፡ ነገር ፡ አስተውሉ ።

፱ ፡ እሉ ፡ ቀዳሚ ፡ ይኄይስ ፡ ብሂል ፡
ነገሮሙ፡ ለእሉ ፡ ሲል ፡ ነው ።
የአበው ፡ ነገራቸው ፡ ከዘጠኙ ፡
ሕገጋት ፡ ኢታምልክ ፡ ይበል
ጣል ፡ ማለት ፡ ነው ።
ወደኃርያንሂ ፡ ኢንከልእ ፡ ርእሳ ፡
ለጥበብ ።
ደኃርያን ፡ ውሉድም ፡ ከዘጠኙ ፡
ሕገጋት ፡ ኢታምልክ ፡ ትበልጣ
ለች ፡ ማለትን ፡ አንከለክልም ።
አንድም ፡ እሉ ፡ ቀደምት ፡ ይኄ
ይሱ ፡ ብሂል ፡ ነገርየ ፡ ይላል ።
የእኔ ፡ ነገሬ ፡ አበው ፡ ኢታምል
ክን ፡ በመጠበቅ ፡ ይበልጡናል ፡
ማለት ፡ ነው ።
ወደኃርያንሰ ፡ ኢንከል ።
ደኃርያን ፡ ውሉድ ፡ እኛ ፡ ግን
የዘጠኙ ፡ አበጋዝ ፡ ኢታምልክን
መጠበቅ ፡ አንችልም ።
[redacted] ፡ ወእስከ ፡ ይእዜ ፡ ኢተውህበኒ ፡
እምቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፡
ዘንሣእኩ ፡ ጥበበ ፡ ዘከመ ፡ ሐለይኩ ፡
በከመ ፡ ፈቀደ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት
ዘተውህበኒ ፡ እምኔሁ ።
ጥበብን ፡ የተቀበልሁት ፡ መቀ
በል ፡ አንድም ፡ በጥበብ ፡ የተቀ
በልሁት ፡ አንድም ፡ ጥበብ ፡ ቢል ፡
የተቀበልሁት ፡ ጥበብ ፡ እኔ ፡ እንደ
ወደድሁ ፡ እንደ ፡ አሰብሁ ፡ እስከ
ዛሬ ፡ ድረስ ፡ በእግዚአ ፡ መናፍስት፡
ፊት ፡ አልተሰጠኝም ።
ክፍለ ፡ ሕይወት ፡ ዘለዓለም ።
የዘለዓለም ፡ ዕድል ፡ የሚሆን ፡

ከእግዚእ ፡ መናፍስት ፡ የተሰ
ጠኘ ፡ ጥበብ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡
ድረስ ፡ አልተሰጠኘም ፤
፮ ፤ ወኮኑ ፡ ብየ ፡ ፫ቱ ፡ ምሳሌያት ፤
ሦስቱ ፡ ነገራት ፡ ተገለጹልኝ ፤
ሁለቱ ፡ ነገራት ፡ ናቸው ፤ አንዱ ፡
ምሳሌ ፡ ነው ፤ ከዚያም ፡ ነገር ፡
አለበት ፤ አጸምዕ ፡ ምሳሌ ፤
በእዘንየ* ፤ እንዲል ፤
፯ ፤ ወአንስ ፡ እብሎሙ ፡ ለእለ ፡
የኀድሩ ፡ ዲበ ፡ የብስ ፤
እኔም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ላሉ ፡
ሰዎች ፡ እነግራቸው ፡ ጀመር ፤
፰ ፤ ምሳሌ ፡ ቀዳሚ ፡ ሶበ ፡ ያስተ
ርኢ ፡ ማኅበረ ፡ ጻድቃን ፤
መጀመሪያው ፡ ነገር ፡ ይህ ፡
ነው ፤ የደጋጎች ፡ ማደሪያ ፡
በተገለጠ ፡ ጊዜ ፤
ወይትኴነኑ ፡ ኃጥአን ፡ በኃጢአቶሙ፡
ኃጥአንም ፡ በኃጢአታቸው ፡
በተፈረደባቸው ፡ ጊዜ ፤
ወእምገጸ ፡ የብስ ፡ ይትሐወኩ ፤
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ይጠፋሉ ፤
፱ ፤ ወሶበ ፡ ያስተርኢ ፡ ጻድቅ ፡
በገጾሙ ፡ ለጻድቃን ፡ እለ ፡ ኅሩያን ፡
ተግባሮሙ ፡ ስቁል ፤ በእግዚእ ፡ መና
ፍስት ፤
ጻድቀ ፡ ባሕርይ ፡ ክርስቶስ ፡
ጌታ ፡ ለእነርሱ ፡ ያደረገው ፡ ነገር ፡
በጸናላቸው ፡ ጊዜ ፤ አንድም ፡
እነርሱ ፡ ለእርሱ ፡ ብለው ፤
ያደረጉት ፡ በጸናላቸው ፡ ጊዜ ፤

፲ ፤ ወያስተርኢ ፡ ብርሃን ፤ ለጻድቃን፡
ወለኅሩያን ፡ እለ ፡ የኀድሩ ፡ ዲበ ፤
የብስ ፤
በዚህ ፤ ዓለም ፡ ለሚኖሩ ፡ ለደ
ናግልና ፡ ለሕጋውያን፡ ብርሃን ፤
መለኮቱ ፡ በተገለጠ ፡ ጊዜ ፤
፲፩ ፤ አይቴ ፡ ማኅደረ ፡ ኃጥአን ፡
ወአይቴ ፡ ምዕራፎሙ ፡ ለእለ ፡
ክህድዎ ፡ ለእግዚእ ፡ መናፍስት ፤
የነፍሳት ፡ ጌታን ፡ የካዱት ፡ ሰዎች ፡
ቦታቸው ፡ ወዴት ፡ ነው ? የኃጥአን፡
ማደሪያቸውስ ፡ ወዴት ፡ ነው ?
፲፪ ፤ እምኀየሶሙ ፡ ሶበ ፡ ኢተወ
ልዱ ፤
ጥንቱን ፡ ባይፈጠሩ ፤ በተሻላ
ቸው ፡ ነበር ፤
ወሶበ ፡ ይትከሠታ ፤ ኅቡዓቲሆሙ ፡
ለጻድቃን ፡ ይትኴነኑ ፡ ኃጥአን ፤
ስውረው ፡ ያደረጉት ፤ አንድም
ሰውሮ ፤ ያደረገላቸው ፡ የጻድ
ቃን ፡ ክብራቸው ፡ በተገለጠ ፤
ጊዜ ፤ በኀጢአተኞች ፡ ይፈረ
ድባቸዋል ፤
ወይትሀወኩ ፡ ረሲዓን ፡ እምገጸ ፡
ጻድቃን ፡ ወኅሩያን ፤
ደናግልንና ፡ ሕጋውያንን ፡ ከመ
በደላቸው የተነሣ ፡ ሕግን ፡
የዘነጉ ፡ ሰዎች ፡ ይታወከሉ ፤
፲፫ ፤ ወእምይእዜ ፡ ኢይከውኑ ፡ እዚ
ዛነ ፡ ወኢልዑላነ ፤ እለ ፡ ይእኅዝዋ ፡
ለምድር ፤
እንግዲህ ፤ ወዲህ ፡ ይህችን ፤
ዓለም ፡ የሚገዙ ፡ ሰዎች ፡

፩ መዝ. ፵፰ ፥ ፬

ከዛሬ ፡ ጀምሮ ፡ ጹኑዓን ፡ ክቡራን ፡ አይሆኑም ፤

፲፩ ፤ ወኢይክሉ ፡ ርእየ ፡ ገጸ ፡ ቅዱሳን ፤

የቅዱሳንን ፡ ፊት ፡ ሲያዩ ፡ አይ ችሉም ፡

እስመ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ተርእየ ፡ ብርሃኑ ፡ ለገጸ ፡ ቅዱሳን ፡ ጻድቃን ፡ ወኅሩያን ፤

ለደናግልና ፡ ለከበሩት ፡ ሕጋው ያን፡ የመላእክት ፡ጌታ ፡ ብርሃን፡ መስኮቱ ፤ አንድም ፡ የባሕርይ ፡ ክብሩ ፡ ተገልጿልና ፡ የቅዱሳንን፡ ፊት ፡ ማየት ፡ አይችሉም ፤

፲፭ ፤ ወነገሥት ፡ አዚዛን ፡ በውእቱ ፡ ጊዜ ፡ ይትኀጐሉ ፡ ወይትወሀቡ ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ ጻድቃን ፡ ወቅዱሳን ፤

በጻድቃን ፡ እጅ ፡ የሚፈረድባ ቸው ፡ ሆኖ ፡ አይደለም ፤ ጻድ ቃንን ፡ በበደሉበት ፡ በደል ፡ የሚፈርድባቸው ፡ ስለሆነ ፤

፲፮ ፤ ወእምህየ ፡ አልቦ ፡ ዘያስተም ህር ፡ ሎሙ ፡ ኀበ ፡ እግዚእ ፡ ስብ ሐት ፡ እስመ ፡ ተወድአ ፡ እንቲአሆሙ ፡ ሕይወት ፤

የእነርሱ ፡ የሚሆን ፡ ደኅንነታ ቸው ፡ ጨርሶ ፡ ጠፍቷልና ፡ ከዚያ ፡ ከመከራው ፡ በመላእክት ጌታ ፡ ዘንድ ፡ ለእነርሱ ፡ የሚያ ማልድ ፡ የለም ፤

፲፯ ፤ ወይከውን ፡ በዝንቱ ፡ መዋ ዕል ፡ ይወርዱ ፡ ደቂቅ ፡ ኅሩያን፡ ወቅዱሳን ፡ እምልዑላን ፡ ሰማያት ፤

በዚያ ፡ ወራት ፡ እንዲህ ፡ ይሆናል ፤ ከልዑል ፡ መዓርግ ፤ ከደብር ፡ ቅዱስ ፤ ከሰማያዊ ፡ ግብር ፡ የወረዱ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ገዛነም ፡ ይወርዳሉ ፤

ወአሐደ ፡ ይከውን ፡ ዘርዖሙ ፡ ምስለ ውሉደ ፡ ሰብእ ፤

ልጆቻቸው ፡ ከቃየል ፡ ልጆች ፡ ጋር ፡ አንድ ፡ ይሆናሉ ፤

፲፰ ፤ ወበውእቱ ፡ መዋዕል ፡ ነሥአ ፡ ሄኖክ ፡ መጻሕፍተ ፡ ቅንአት፤ወመዓት ፤

ባልንጀራ ፡ ለባልንጀራው ፡ ቀንቶ፡ የሚሠራው ፡ ኃጢአት ፡ የተጻፈ በት ፤ አንድም ፡ ለአምላክነቱ ፡ ቀንቶ ፡ የሚያመጣው ፡ መቅሠ ፍት ፡ የተጻፈበት ፡

ወመጻሕፍተ ፡ ጒጒዓ ፡ ወሀውክ ፤

ለሞት ፡ ለመከራ ፡ የሚያስቸ ኩል ፡ መከራ ፡ የተጻፈበትን ፡ መጽሐፍ ፡ ሄኖክ ፡ አነሣ ፤

፲፱ ፤ ወምሕረት ፡ ኢይከውን ፡ ላዕሌ ሆሙ ፡ ይቤ ፡ እግዚእ ፡ መናፍስት ፤

የመላእክት ፡ ጌታ ፡ ይቅርታ ፡ አያደርግላቸውም ፡ አለ ፤

፳ ፤ ወበውእቱ ፡ ጊዜ ፡ መሠጠኒ ፡ ደመና ፡ ወአውሎ ፡ ነፋስ ፡ እምገጸ ፡ ለምድር፤

በዚያም ፡ ጊዜ ፡ ጥቅል ፡ ነፋ ስና ፡ ደመና ፡ ከዚህ ፡ዓለም ፡ ወሰደ ፤

ወአንበረኒ፡ ውስተ ፡ ጽንፈ፡ ሰማያት፤

በሰማይ ፡ ዳርቻ ፡ በአድማስ ፡ አኖረኝ ፡
፳፩ ፤ ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ካልአ ፡ ራእየ፤
በዚያም ፡ ቦታ ፡ ሌላ ፡ ራእይ ፡ አየሁ ፤
ማኅደሪሆሙ ፡ ለጻድቃን ፡ ወምስካባቲሆሙ ፡ ለቅዱሳን ፤
የጻድቃንን ፡ ማደሪያቸውን ፡ የቅዱሳንን ፡ ቦታቸውን ፡ አየሁ ፤
፳፪ ፤ ወበህየ ፡ ርእየ ፡ አዕይንትየ ፡ ማኅደሪያሆሙ ፡ ምስለ ፡ መላእክት ፤
ከዚያም ፡ ቦታ ፡ ዓይኖቼ ፡ ከመላእክት ፡ ጋራ ፡ የሚኖሩበት ማደሪያቸውን ፤ ወምስካባቲሆሙ፡ ምስለ ፡ ቅዱሳን ፤ ከቅዱሳንም ፡ ጋራ ፡ የሚኖሩበትን ፡ ቦታቸውን ፡ አዩ ፤
፳፫ ፤ ወይስእሉ ፡ ወያስተበቍዑ ፡ ወይጼልዩ፡ በእንተ፡ ውሉደ ፡ ሰብእ ፤
ስለ ፡ ሰውም፡ ልጆች ፡ ፈጽመው፡ ይለምናሉ ፡ ይማልዳሉ ፤ ይጸልያሉ ፤
፳፬ ፤ ወጽድቅ ፡ ከመ ፡ ማይ ፡ ይውኅዝ ፡ በቅድሜሆሙ ፤
ቸርነት ፡ በፊታቸው ፡ እንደ ፡ ውሀ ፡ ይፈስሳል ፡ (በዝቶ ፡ ይሰጣል) ፡ ሲል ፡ ነው ፡
ወምሕረት ከመ ፡ ጠል ፡ ውስተ ፡ ምድር ፤
ይቅርታም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ እንደ ፡ ጠል ፡ ይሆናል ፤ በዝቶ ይሰጣል ፤
ከመዝ ፡ ውእቱ ፡ ማዕከሎሙ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤
ጻድቃን ፤ መላእክት ፤ በሚያማልዱት ፡ ምልጃ ፡ ራሳቸውንም፤ ሰውንም ፡ ጠቅመው ፡ ለዘላለሙ ፡ ይኖራሉና ፤
፳፭ ፤ ወበውእቱ ፡ መዋዕል ፡ ርእያ፡ አዕይንትየ ፡ መካነ ፡ ኅሩያን ፡ ዘጽድቅ ወዘሃይማኖት ፤
በምግባር ፡ በሃይማኖት ፡ ጸን ተው ፡ የሞቱ ፡ የጻድቃንን ፡ ቦታ ፡ አየሁ ፤
፳፮ ፤ ወጽድቅ ፡ ይከውን ፡ በመዋዕ ሊሆሙ ፡ ለጻድቃን ፡ ወለኅሩያን ፡ አልቦሙ ፡ ኍልቍ ፡ ቅድሜሁ ፡ ለዓ ለመ ፡ ዓለም ፤
በዘመናቸው ፡ ቸርነቱ ፡ ይደረ ግላቸዋል ፤ ለተመረጡ ፡ ጻድ ቃን ፡ ለሚኖሩት ፡ ዘመን ፡ ፍጻሜ ፡ የለውም ፤ እንድም ፡ ለጻድቃን፡ ቍጥር ፡ የላቸውም ፡
፳፯ ፤ ወርኢኩ ፡ ማኅደርሙ ፡ መት ሕተ ፡ አክናፈ ፡ እግዚእ ፡ መናፍስት፤
በእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ አጠገብ የተያዘ፡ ማደሪያቸውን ፡ አየሁ ፤
፳፰ ፤ ወኵሎሙ ፡ ጻድቃን ፡ ወኅሩ ያን ፡ በቅድሜሁ ፡ ይትለሐዩ ፡ ከመ ፡ ብርሃነ ፡ እሳት ፤
ያበርሁ ፡ ሲል ፡ ነው፤ ደናግልና ሐጋውያንም ፡ ሁሉ ፡ በፊቱ ፡ እንደ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ብር ሃን ፡ ያበራሉ ፤

፳፱ ፤ ወአፉሆሙ ፡ ይመልዕ ፡ በረ
ከተ ፡ ወከናፍሪሆሙ ፡ ይሴብሕ ፡
ስሞ ፡ ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፡ ወጽ
ድቅ ፤

አፉቸው ፡ በረከትን ፡ (ምስጋናን)፡
ይመላል ። ከንፈሮቻቸውም ፡
የመላእክት ፡ ጌታን ፡ ስም ፡
ያመሰግናሉ ፤ አንድም ፡ ስሙን፡
ያመሰግኑት ፤ ዘንድ ፤ አንድም ፡
በስሙ ፡ አምነው ፡ ያመሰግኑት፡
ዘንድ ፤

፴ ፤ ወጽድቅ ፡ ቅድሜሁ ፡ ኢየሐ
ልቅ ።

በፊቱ ፡ የሚሰጥ ፡ ቸርነት ፡ አያ
ልቅም ፡

ወርትዕ ፡ ቅድሜሁ ፡ ኢየሐልቅ ፤
በርትዓተ ፡ ሕሊና ፡ የሚገኘው ፡
ክብርም ፡ በፊቱ ፡ ፍጻሜ ፡ የለ
ውም ፤

፴፩ ፤ ወበህየ ፡ ፈቀድኩ ፡ እኅድር ፡
ወፈተወቶ ፡ ነፍስየ ፡ ለውእቱ ፡
ማኅደር፤

በዚያም ፡ ቦታ ፡ እኖር ፡ ዘንድ
ወደድሁ ። ያንንም ፡ ቦታ ፡
ልቡናዬ ፡ ወደደችው ፤

፴፪ ፤ በህየ ፡ ኮነ ፡ ክፍልየ ፡ ቅድመ፤
እኔ ፡ በከንቱ ፡ እንዲህ ፡ አልሁ፡
እንጂ ፡ ጥንቱም ፡ ዕድል ፡ ፈን
ታዬ ፡ በዚህ ፡ ሆነ ፤

እስመ ፡ ከመዝ ፡ ጸንዐ ፡ በእንቲአየ ፡
በቅድመ ፡ እግዚአ ፡ መናፍስት ፤
በመላእክት ፡ ጌታ ፈቃድ ፡
ስለእኔ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማይ ፡
ጸንቷልና ፤ እስመ ፡ በእንቲአክሙ ፤
ፈጠርኩዎ ፡ ለዓለም ፡ እንዲል ፡

፴፫ ፤ ወበውእቶን ፡ መዋዕል ፡ ሰባ
ሕኩ ፡ ወአልዐልኩ ፡ ስሞ ፡ ለእግዚአ፡
መናፍስት ፤

በዚያም ፡ ወራት ፡ የመላእክት
ጌታን ፡ ስም ፡ አክብሬ ፡ አመ
ሰገንኩ ፤

በረከተ ፡ ወስብሐተ ፡ ወሀብኩ ፤
እስመ ፡ ውእቱ ፡ አጽንአኒ ፡ በበረከት
ወስብሐት ፡ በከመ ፡ ፈቃዱ ፡
ለእግዚአ ፡ መናፍስት ፤

የመላእክት ፡ ጌታ ፡ እንደ ፡
ወደደ ፤ በፍጹም ፡ ምስጋና ፡
እርሱ ፡ አጽንቶኛልና ፡ ፍጹም ፡
ምስጋናን ፡ አቀረብሁ ፤

፴፬ ፤ ወኍንዱየ ፡ ርእያ ፡ አዕይንትየ፡
በውእቱ ፡ መካን ፤

ዓይኖቼ ፡ ቅዝ ፡ ብለው ፡ ያያሉ
እንደ ፡ ገጠር ፡ ሰው ። ከተማ ፡
ቢዶ ፡ ቅዝ ፡ ብሎ ፡ እንዲያይ ፤

፴፭ ፤ ወባረክዎ ፡ ወሰባሕክዎ ፡
እንዘ ፡ እብል ፡ ቡሩክ ፡ ውእቱ ፡
ወይትባረክ ፡ እምቅድመ ፡ ዓለም ፡
ወእስከ፡ ለዓለም ፤

የተመሰገነ ፡ ነው ፤ ከጥንት ፡
ጀምሮ ፡ እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡
ይክበር ፡ ይመስገን ፡ እያልኩ ፡
ፈጽሜ ፡ አመሰገንሁት፤

፴፮ ፤ ወበቅድሜሁ ፡ አልቦ ፡ ማኅለ
ቅት ፤

በፊቱም ፡ ለሚደረገው ፡ ቸርነት
ፍጻሜ ፡ የለውም ፤

፴፯ ፤ ውእቱ : የአምር : ዘእንበለ : ይትፈጠር : ዓለም : ምንት: ውእቱ: ዓለም ፤
ዓለም : ሳይፈጠር : ይህ : ዓለም : ምን : እንደሆነ : እርሱ : ያውቃል ፤
ወለትውልደ : ትውልድ : ዘይከውን : ለልጅ : ልጅ : ዘመን : የሚሆነውን : ነገር : ያውቃል ፤
፴፰ ፤ ይባርኩከ : እለ : ኢይነውሙ : ወይቀውሙ : በቅድመ: ስብሐቲከ ፤
የማያርፉ ፤ በጌትነትህም : ፊት: የሚቆሙ : መላእክት : ያመሰግኑሃል ፤
፴፱ ፤ ወይባርኩ : ወይሴብሑ : ወያሌዕሉ : እንዘ : ይብሉ : ቅዱስ : ቅዱስ: ቅዱስ: እግዚአ : መናፍስት ፤
የመላእክት : ጌታ : ንጹሕ ፤ ክቡር : ልዩ : አንተ : ነህ : እያሉ : ፈጽመው : ያመሰግናሉ: ከፍ : ከፍም : ያደርጋሉ ። ቅዱስ ፤ ቅዱስ ፤ ቅዱስ : ብሎ ሦስትነቱን ፤ እግዚአ : መናፍስት : ብሎ : አንድነቱን : ተናገረ ፤ አንድም : ቅዱስ : ብሎ : ፩ነቱን : ተናገረ ፤ ለ፫ቱ : ሁሉ : ልብ : ቃል : እስትንፋስ : ቢኖራቸው : ቅዱሳን : ቅዱሳን : ባለ : ነበርና : ቅዱስ : ቅዱስ : ቅዱስ : ብሎ : ፫ት : ጊዜ : መናገሩ : የ፫ነቱ : ነው ፤
ወይመልእ : ምድረ : መናፍስት ፤
ፍጥረታት : ያሉባትን : ምድር በምልዓት : ይመላል ፤ አንድም: ምድረ : መናፍስተ : ቢል : ፍጥረታትን : በምድር : ይመላል፤ አንድም : ምስጋናን : በምድር : ይመላል ፤
፵ ፤ ወበህየ : ርእያ : አዕይንትየ : ኵሎ : እለ : ኢይነውሙ : ይቀውሙ : ቅድሜሁ : ወይባርኩ ፤
በዚያም : ቦታ : የማያርፉ : መላእክትን : ሁሉ : በፊቱ : ቁመው : ሲያመሰግኑ : ዓይኖቼ : አዩ ፤
፵፩ ፤ ወይብሉ : ቡሩክ : አንተ : ወቡሩክ : ስሙ : ለእግዚአ : መናፍስት : ለዓለመ : ዓለም ፤
አንተ : የከበርክ : ነህ ፤ የመላእክት : ጌታ : ስሙም : ለዘለ ዓለም : የከበረ : ነው : ይላሉ ፤
፵፪ ፤ ወተወለጠ : ገጽየ : እስከ : ስእንኩ : ነጽሮ ፤
ቀና : ብሎ : ማየት : እስኪሳነኝ : ድረስ : ዓይነ : ልቡናዬ : ተለወጠ ።

## ምዕራፍ ፲

፩ ፤ ወርኢኩ : እምድኅረዝ : አእላፈ አእላፋት : ወትእልፊተ : አእላፋት ፤
ከዚህም : በኋላ : ፈጽመው : የበዙ : የብዙ : ብዙ : የሚሆኑ መላእክትን : አየሁ ፤
ወአልቦሙ : ኍልቍ : ወሐሳብ : ለእለ : ይቀውሙ : ቅድመ : እግዚአ መናፍስት ፤